ባቸው መንገዶችና የዲሞክራሲያዊ ማእከላዊነት መርሕ ተፈጻሚ የሚሆኑበት ሁኔታዎች በሚገባ ተገልጸዋል ።

ኢሕዲሪ የሠርቶ አደሩን ሕዝብ ጥቅም የሚያስከብርና የብሔረሰቦችን እኩልነት የሚያ ረጋግጥ አሐዳዊ መንግሥት መሆኑም ተደንግጓል ። የአገሪቱ ባለቤት የሆኑ የሁሉም ብሔረሰቦች ሠርቶ አደሮች በመንግሥት ሥልጣን ውስጥ በእኩልነት የሚሳተፉ መሆናቸው ከመደንገጉም በላይ የአካባቢ የራስ በራስ አስተዳደርን ተግባራዊ የማድረጊያ ስልቶች በረቂቁ ላይ ተመልክ ተዋል ። በተጨማሪም ለጋራ ዕድገት መፋጠንና ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ መደባዊ አንድነት መጠና ከር የጋራ መግባቢያ ቋንቋ በማስፈለጉ አማርኛ የመንግሥት የሥራ ቋንቋ መሆኑ በክፍል አራት ተደንግጐ የሁሉም ብሔረሰቦች ቋንቋዎች በእኩልነት የሚታዩበት ፣ የሚዳብሩበትና የሚከበሩበት ሁኔታ በዚሁ ክፍል አንቀጾች ሕገ መንግሥታዊ ዋስትና አግኝቷል ።

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የሚያራምደው የኢኮኖሚ ሥርዓት የም ርት ኃይሎችን እድገት በማፋጠን ኢኮኖሚውን ከኋላቀርነት ለማላቀቅና ለሶሻሊስት የምርት ግንኙነት መሠረት ለመጣል የሚያስችል ነው ። በዚህ ሥርዓት ሶሻሊስት ባለቤትነት ማለ ትም የመንግሥትና የኅብረት ሥራ ማኅበራት ባለቤትነት በኢኮኖሚው ውስጥ የጐላ ሚና የተ ሰጣቸው ሲሆን የግልና ሌሎች የባለቤትነት ዓይነቶችም ተገቢውን ትኩረት አግኝተዋል ።

የኢሕዲሪን ማኅበራዊና ባህላዊ ፖሊሲ በሚመለከተው ምዕራፍ ውስጥ የተደነገገውም ኢትዮጵያውያን የተሟላ ማኅበራዊ ዋስትና አግኝተው ፣ በአካልና በአእምሮ ዳብረው ብቁ ዜጐች እንዲሆኑ የሚያግዝ ከመሆኑም በላይ በረጅም ዘመናት የተካበቱትን ታሪካዊ ቅርሶች ለመጠበቅና ሠርቶ አደሩን ሕዝብ ከፊውዳሉ ሥርዓት ከተወረሱ ጐጂ ባህሎች በማላቀቅ ደረጃ በደረጃ ወዛደራዊ ባህልን ለማስፈን የሚያስችል ነው ።

የኢሕዲሪ የመከላከያ ኃይል ዐብይ ተግባር የመንግሥቱን ሉዓላዊነትና የግዛት አንድ ነት እንደዚሁም አብዮቱን መጠበቅ ሲሆን የመከላከያ ኃይሉ አደረጃጀትና በዚህ ውስጥ የሠ ርቶ አደሩ ታሪካዊ ኃላፊነት ይሆን ጉዳይ በሚመለከተው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ምዕራፍ በሚገባ ተንጸባርቋል ።

በዚህ ክፍል ውስጥ ከተጠቃለሉት ዋና ዋና ጉዳዮች አንዱ የኢሕዲሪ የውጭ ፖሊሲ ነው ። ኢሕዲሪ የሚከተለው የውጭ ፖሊሲ በወዛደራዊ ዓለም አቀፋዊነት ፣ በገለልተኝነትና በሰ ላም አብሮ መኖር መርሖች ላይ የተመሠረተ መሆኑን በግልጽ የሚደነግጉ አንቀጾች በዚሁ የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ምዕራፍ ውስጥ ሰፍረዋል ።

በሕዝባዊ ውይይቱ ወቅት ሥርዓተ ማኅበሩን በሚመለከተው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ክፍል ከቀረቡት ጥያቄዎች ፣ አስተያየቶችና ሐሳቦች መካከል ጥቂቱን ለማመልከት ፦
—ሥልጣን የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ነው ማለት ምን ማለት ነው ?
—በፓርቲና በመንግሥት መካከል የሚኖረው ግንኙነት በአፈጻጸም ምን መልክ ይኖረዋል ?
—ለግል ባለቤትነት ሕገ መንግሥታዊ ዋስትና መስጠት ለምን አስፈለገ ?
—የመከላከያ ኃይሉ ልዩ ልዩ ተቋሞች በሕገ መንግሥቱ ይገለጡ !
—ገለልተኝነትና ወዛደራዊ ዓለም አቀፋዊነት አይጋጩምን ?
የሚሉና የመሳሰሉት ይገኛሉ ።

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሰፊ ማኅበራዊ መሠረት ያለው መንግ ሥት ነው ። የሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነት መግለጫ የሆኑ አካላትና በነዚህም ውስ ጥ በቀጥታ ለመሳተፍ የሚችሉ የኅብረተሰብ ክፍሎች በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ልዩ ልዩ አንቀጾች በግልጽ ሰፍረዋል ። ስለእነዚህ አካላት ሥልጣንና ተግባር እንዲሁም ስለአሠራራቸው በመናኛ ነት ወይም በምንጭነት የሚያገለግሉ መሠረታዊ ጉዳዮች በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ የተመለከቱ ሲሆን ሌሎቹ ጉዳዮች በእነዚህ ላይ በመመሥረት በሚወጡ ዝርዝር ሕጐች የሚሸፈኑ ይሆናሉ ።

በዚሁ ክፍል አንቀጽ ፩፻፰ (የቀድሞው አንቀጽ ፩፻፮) ላይ የትርጉም አገልግሎት በፍርድ ቤት ለተገኘ «ለማንኛውም ሰው» የሚሰጥ ስለሚያስመስል አገልግሎቱ በፍርድ ቤቶች ከሚታዩ ጉዳዮች ጋር የቅርብ ተዛምዶ ላላቸው ብቻ እንደሚሰጥ በሚያመለክት መልኩ ይስተካከል የሚል ትክክለኛ አስተያየት ከሕዝቡ ውይይት ተገኝቷል ። ኮሚሽኑም ይኸንኑ አስተያየት መሠረት በማድረግ «ማንኛውም ሰው» ይል የነበረው «ባለጉዳይ» በሚለው እንዲስተካከል በመወሰኑ «ፍርድ ቤቶች የዳኝነት ተግባራቸውን የሚያከናውኑበትን ቋንቋ ለማይችል ማንኛውም ሰው የትርጉም አገልግሎት ይሰጣሉ ።» ይል የነበረው ፣

«ፍርድ ቤቶች የዳኝነት ተግባራቸውን የሚያከናውኑበትን ቋንቋ ለማይችል ባለጉዳይ የትርጉም አገልግሎት ይሰጣሉ ።»

እንዲል ሆኖ ተሻሽሏል ።

## 3.5 ክፍል አራት–ጠቅላላ ድንጋጌዎችን በሚመለከት

በዚህ የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ክፍል ውስጥ የአገሪቱን ሰንደቅ ዓላማ ፣ አርማ ፣ መዝሙር ፣ የመንግሥት የሥራ ቋንቋና ርእሰ ከተማን እንዲሁም ስለ ሕገ መንግሥቱ ሕጋዊ ኃይልና ስለሚሻሻልበት ሥርዓት የሚደነግጉ አንቀጾች ሰፍረዋል ።

በመሠረቱ የዚህ ክፍል የመጀመሪያው ምዕራፍ የሚደነግጋቸው ጉዳዮች የሪፑብሊኩ መግለጫ ምስሎች ናቸው ። እነዚህም ምስሎች የሪፑብሊኩ ሉዓላዊነትና ባሕርያት የሚገለጡባቸውና ሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነቱን ተግባራዊ የሚያደርግበትን የፖለቲካ ማዕከል የሚያሳዩ ምልክቶች ናቸው ። በዚህ የክፍሉ ምዕራፍ ውስጥ ከተደነገጉት የጥቂቶቹ ( ለምሳሌ ፦ አርማ ፣ ብሔራዊ መዝሙር ) ይዘት በዝርዝር ሕግ እንደሚወሰን ተደንግጓል ። ዝርዝር ሕጎቹ በሚወጡበት ጊዜ የእነዚህ ይዘት የሪፑብሊኩን መሠረታዊ ባሕርያት እንደሚያንጸባርቁ የሚጠበቅ ሲሆን በወቅቱም ለሕዝቡ ይፋ የሚሆኑ ናቸው ።

በውይይቱ ወቅት በዚህ የሕገ መንግሥቱ ክፍል ውስጥ ከተነሱት ጥያቄዎች ጥቂቶቹ ፦

—አርማውና መዝሙሩ በሕገ መንግሥቱ ለምን አይገለጹም ?

—አማርኛ የመንግሥት የሥራ ቋንቋ ሆኖ መደንገጉ ከቋንቋዎች እኩልነት ፣ መዳበርና መከበር ጋር እንዴት ይታያል ? *

—አዲስ አበባ ርእሰ ከተማ መሆኗ እየታወቀ በሕገ መንግሥቱ መደንገግ ለምን አስፈለገ ?

የሚሉና የመሳሰሉ ናቸው ።

አዲስ አበባ በታሪክ ባገኘችው እድገት ላይ በመመሥረት የአገሪቱ ማዕከል ሆና መቆየቷ ይታወቃል ። የሪፑብሊኩ የፖለቲካ ማዕከል መሆኗም የሚቀጥል ሲሆን በዚህም ምክንያት የምታስተናግዳቸው እያሌ የአገር ውስጥ ፣ አህጉራዊና ዓለም አቀፋዊ ጉዳዮች ይኖራሉ ። ይህ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነት መግለጫ የሆነው ብሔራዊ ሸንጎና ሌሎች አገሪቱን የሚመሩ የሥልጣንና የአስተዳደር አካላት ተግባራቸውን የሚያከናውኑበት ማዕከል በሕገ መንግሥቱ በግልጽ መመልከቱ ተገቢ ይሆናል ።

አርማውንና መዝሙሩን በተመለከተ የቀረቡት ጥያቄዎች በአብዛኛው ቅርጽንና ግንዛቤን የሚመለከቱ ናቸው ። የነዚህ ዝርዝር ይዘት በሕገ መንግሥቱ አለመገለጽ የሚያስከትለው ችግር አይኖርም ። ከእነዚህ ጋር የተነሱ ግንዛቤን የሚመለከቱ ጥያቄዎች በወቅቱ በተደረጉ ማብራሪያዎች ተገቢውን ምላሽ አግኝተዋል ።

---

* ስለዚህ ጉዳይ በገጽ 34 የተባለውን ይመልከቱ ።

የቀረቡ አስተያየቶች ትክክል ሆኖ ስላገኛቸው «የሚኒስትሮች ምክር ቤትን ይሰበስባል ፤» ይል የነበረው ንዑስ አንቀጽ (፩) ፣

«የሚኒስትሮች ምክር ቤትን ይሰበስባል ፤ ሥራውን ይመራል ፣ ያስተባብራል ፤»

እንዲል ሆኖ ተስተካክሏል ።

በዚሁ አስተያየት ላይ በመመሥረት «የሚኒስትሮች ምክር ቤትን ይወክላል ፤ ሥራውን ይመራል ፣ ያስተባብራል ፤» ይል የነበረው ንዑስ አንቀጽ (፪) ፣

«የሚኒስትሮች ምክር ቤትን ይወክላል ፤»

እንዲል ሆኖ ተሻሽሏል ።

በሕዝብ ውይይት ወቅት ከተነሱት ጥያቄዎችና አስተያየቶች መካከል አንዱ በአስተዳደር አካባቢዎችና በራስ ገዝ አካባቢዎች ደረጃ ስለ አካባቢ ሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴዎች ምንም የተጠቀሰ የለምና ይህ ለምን ሆነ ? የሚል ይገኛል ። በመሠረቱ የሠርቶ አደሩ ቁጥጥር ኮሚቴ ዎች በብሔራዊ ደረጃ ብቻ ሳይሆን በየደረጃውና በልዩ ልዩ ተቋሞች ውስጥ ተመሥርተው በሕግ የተሰጣቸውን ተግባርና ኃላፊነት በመወጣት ላይ ይገኛሉ ። ይህ ከሪፑብሊኩ ምሥረታ በኋ ላም በተጠናከረ መልክ የሚቀጥል ይሆናል ። በየደረጃው የሚቋቋሙ የሠርቶ አደሩ ቁጥጥር ኮሚቴ ዎች አደረጃጀት ፣ ሥልጣንና ተግባር እንዲሁም ሌሎች ከእነዚህ ጋር የተያያዙ ጉዳዮች በሕገ መንግሥቱ ላይ ተመሥርተው በሚወጡ ሌሎች ሕጎች የሚደነገጉ ይሆናሉ ። ይህ እንደተጠ በቀ ሆኖ በብሔራዊ ደረጃ የሚቋቋመው የሠርቶ አደሩ ቁጥጥር ኮሚቴ ሊቀ መንበር በብ ሔራዊ ሸንጎ እንደሚመረጥ በአንቀጽ ፷፫ ንዑስ አንቀጽ ፬ (ሠ) ተደንግጓል ። በአካባቢ ደረጃ የሚቋቋሙ የሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴዎችም ከሚኖራቸው ከፍተኛ ኃላፊነትና የሕዝብ አደራ አንፃር ሊቀ መንበሮቻቸው በየደረጃው በሚገኙ ሸንጎዎች እንደሚመረጡ በሕገ መንግ ሥቱ መደንገጉ ተገቢ መሆኑ ታምኖበታል ። ስለዚህም ፦

«የአካባቢውን ሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴ ሊቀመንበር ይመርጣል ፤»

የሚለው የአንቀጽ ፷፯ ንዑስ አንቀጽ (፯) ሆኖ እንዲገባ ተደርጓል ። *

በዚህ ክፍል ውስጥ ከሕዝብ በተገኘው አስተያየት መሠረት ማሻሻያ የተደረገበት ሌላው አንቀጽ ፩፻፩ (የቀድሞው አንቀጽ ፩፻፪ ንዑስ አንቀጽ (፩)) ነው ። ለውይይት በቀረበው ረቂቅ ላይ «የሌሎች ፍርድ ቤቶች ዳኞች» ይል የነበረው የሰፋና ስለየትኞቹ ፍርድ ቤቶች እንደሚደ ነግግ ግልጽ ስላልሆነ መስተካከል ይኖርበታል የሚሉ ትክክለኛ አስተያየቶች ተሠንዝረዋል ። ኮሚሽኑ በዚሁ ላይ በመመሥረት መልዕክቱን በግልጽ ለማስተላለፍ በሚችል መልኩ እ ዲስተካከል ወስኗል ። በዚሁ መሠረት በአንቀጽ ፩፻፩ ንዑስ አንቀጽ (፩) ላይ «ሲሆን የሌሎች» ይል የነበረው «ነው ፤ የአካባቢ» በሚለው ተተክቶ« የጠቅላይ ፍርድ ቤት ዳኞች የሚመረጡት በብሔራዊ ሸንጎ ሲሆን የሌሎች ፍርድ ቤቶች ዳኞች በየአካባቢያቸው ሸንጎዎች ይመረጣሉ።» ይል የነበረው ፤

«የጠቅላይ ፍርድ ቤት ዳኞች የሚመረጡት በብሔራዊ ሸንጎ ነው ፤ የአካባቢ ፍርድ ቤቶች ዳኞች በየአካባቢያቸው ሸንጎዎች ይመረጣሉ ።»

በሚል እንዲስተካከል ተደርጓል ።

ይህ ማስተካከያ መደረጉ እንደተጠበቀ ሆኖ በሕገ መንግሥቱ አንቀጽ ፻ (የቀድሞው አንቀጽ ፩፻፩ ንዑስ አንቀጽ (፩) መሠረት በሕግ የሚቋቋሙ ሌሎች ፍርድ ቤቶች ዳኞች አመ ራረጥ ሁኔታ በሚያቋቁሟቸው ሕጎች የሚሸፈን ይሆናል ።

---

* በዚህም ምክንያት ከአንቀጽ ፷፯ (የቀድሞው አንቀጽ ፷፰) ንዑስ አንቀጽ (፯) ጀምሮ ያሉት ንዑሳን አንቀጾች በአንዳንድ ቁጥር በመጨመር ተሸጋሽገዋል ።

መሆኑ ታምኖበታል ። ስለዚህም «የሚኒስትሮች ምክር ቤት ጠቅላይ ሚኒስትር ፥ ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮች ፥ ኮሚሽነሮችና በሕግ በሚወሰነው መሠረት ሌሎች አባላት የሚገኙበት ምክር ቤት ነው ። » ይል የነበረው አንቀጽ ፹፱ ንዑስ አንቀጽ (፪) ፥

> «የሚኒስትሮች ምክር ቤት ጠቅላይ ሚኒስትር ፥ ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮች ፥ ሚኒስትሮችና በሕግ በሚወሰነው መሠረት ሌሎች አባላት የሚገኙበት ምክር ቤት ነው ።»

እንዲል ሆኖ ተሻሽሏል ።

የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጽ ፺፪ እንዲሻሻል ምክንያት የሆነው ጥያቄ በአንቀጽ ፺፫ ንዑስ አንቀጽ (፩) (ሰ) ላይ በመመሥረት በሕዝብ ውይይት ላይ የቀረበ ጥያቄ ነው ። በዚህ ላይ ተመሥርቶ የቀረበው ጥያቄ የገንዘብና የፋይናንስ ፖሊሲን የመወሰን ሥልጣን የብሔራዊ ሸንጎ መሆኑ ሲደነገግ የሚኒስትሮች ምክር ቤት ከዚህ ጋር ተያይዞ የሚኖረው ኃላፊነት ለምን አልተመለከተም ? የሚል ነው ።

ከገንዘብና ከፋይናንስ ጋር በተያያዘ የሚኒስትሮች ምክር ቤት ከፍተኛ የሥራ ድርሻ እንደሚኖረው ይታወቃል ። ገንዘብና ፋይናንስ ነክ ጉዳዮች ከዕቅድና ከበጀት ዝግጅት ጋር ብቻ በተያያዘ ሳይሆን ከሌሎችም ልዩ ልዩ ተግባራዊ እንቅስቃሴዎች ጋር በመያያዝ የሚከሰቱ ስለሚሆኑ የሚኒስትሮች ምክር ቤት የሥራ ድርሻ እነዚህንም እንዲያካትት ሆኖ መገኘቱን በሕገ መንግሥት ደረጃ ማረጋገጥ አስፈላጊ መሆኑን ኮሚሽኑ አምኖበታል ። ስለዚህም

> «የገንዘብና የፋይናንስ ፖሊሲን ተግባራዊነት ያረጋግጣል ፤»

የሚለው የአንቀጽ ፺፪ ንዑስ አንቀጽ (፯) ሆኖ እንዲገባ ተደርጓል ። *

ለሕዝብ ውይይት ቀርቦ በነበረው ረቂቅ ሰነድ አንቀጽ ፺፪ ንዑስ አንቀጽ (፰) የቀድሞው ንዑስ አንቀጽ (፯) ላይ የሪፑብሊኩን የውጭ ግንኙነት በሚመለከት የሚኒስትሮች ምክር ቤት ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ሐሳብ እንደሚያቀርብ ተመልክቶ ነበር ። በውይይቱ ሂደት የተነሱት ጥያቄዎችና የቀረቡት አስተያየቶች በትክክል እንዳመለከቱት በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በተደነገገው መሠረት የሪፑብሊኩን የውጭ ግንኙነት በሚመለከት ብሔራዊ ሸንጎም ሆነ የመንግሥት ምክር ቤት ድርሻ አላቸው ። ስለዚህም የሚኒስትሮች ምክር ቤት ይህን ጉዳይ በሚመለከት ለነዚህ አካላት ሐሳብ የሚያቀርብ መሆኑን መደንገጉ በሌሎች አንቀጾች ከተመለከቱት ጉዳዮች ጋር የሚጣጣም ከመሆኑም ባሻገር የተሻለ የአሠራር ሁኔታን ለመፍጠር የሚያስችል በመሆኑ በቀረበው አስተያየት መሠረት አንቀጹ መሻሻል ያለበት መሆኑ በኮሚሽኑ ታምኖበታል ። በዚሁ መሠረት « ስለ ሪፑብሊኩ የውጭ ግንኙነት ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ሐሳብ ያቀርባል ፤» ይል የነበረው አንቀጽ ፺፪ ንዑስ አንቀጽ (፰) ፥

> «ስለሪፑብሊኩ የውጭ ግንኙነት ለብሔራዊ ሸንጎ ፥ ለመንግሥት ምክር ቤትና ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ሐሳብ ያቀርባል ፤ ተግባራዊነቱንም ያረጋግጣል ፤»

እንዲል ሆኖ ተስተካክሏል ።

በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ሕዝቡ ውይይት ባደረገበት ወቅት በአንቀጽ ፺፫ ንዑስ አንቀጽ ፩ እና ፪ ላይ ለውጥ እንዲደረግ ምክንያት የሆኑ አስተያየቶችም ቀርበዋል ። በነዚህ ንዑሳን አንቀጾች ላይ ሕዝቡ ያቀረባቸው አስተያየቶች «ምክር ቤቱን መሰብሰብ » እና «ሥራውን መምራትና ማስተባበር» በቅርብ የተያያዙ ሲሆኑ ምክር ቤቱን የመወከሉ ጉዳይ ራሱን የቻለ ተግባር ስለሆነ በዚሁ መልክ ማስተካከያ እንዲደረግ የሚያመለክቱ ናቸው ። ኮሚሽኑ ከሕዝቡ

---

* በዚህም ምክንያት በአንቀጽ ፺፪ (በቀድሞው አንቀጽ ፺፫) ከንዑስ አንቀጽ (፯) ጀምሮ የነበሩ ንዑሳን አንቀጾች አንዳንድ ቁጥር በመጨመር ተሸጋሽገዋል ።

በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ሕዝቡ ውይይት ባደረገበት ወቅት የተነሱትና ለረቂቁ መሻሻል ምክንያት የሆኑት ሌሎች ጥያቄዎችና አስተያየቶች የተመሠረቱት በአንቀጽ ፹፫ ንዑስ አንቀጽ (፪) ላይ ነው ። የጥያቄዎቹና አስተያየቶቹ « የጦር ጊዜ አስተዳደር» እና «ክተት» በዚህ ንዑስ አንቀጽ ላይ የሚሸፈኑ ስለመሆናቸው በግልጽ አይታይምና ማስተካከያ ቢደረግ የሚል መልእክት ያላቸው ናቸው ።

በንዑስ አንቀጹ መሠረት የመንግሥት ምክር ቤት የሚኖረው ሥልጣን « ሸንጐው በማይሰበሰብበት ጊዜ » እና « አስገዳጅ ሁኔታ ሲፈጠር » ተግባራዊ የሚያደርገው ነው ። በተለይ « አስገዳጅ ሁኔታ ሲፈጠር » የሚለው ሐረግ ከሚታወቅ የዕለት ተዕለት ሁኔታ ለየት ያለና የአገርን ፣ የአብዮትን ፣ የመንግሥትና የሕዝብን ደህንነትና ሰላምን የሚነካ ሰው ሠራሽም ሆነ ተፈጥሮአዊ ክስተት ሊያጋጥም የሚችል መሆኑን የሚያመለክት ነው ። እንዲህ ዓይነቱ ክስተት ሲያጋጥም በመንግሥት በኩል ሁኔታውን ለመቆጣጠር የሚወሰዱ የተለያዩ ርምጃዎች ይኖራሉ ። ከነዚህ ዋና ዋናዎቹ በአንቀጽ ፹፫ ንዑስ አንቀጽ (፪) ቢጠቀሱም ሊወሰዱ የሚችሉት ርምጃዎች እነዚሁ ብቻ ሳይሆኑ ከነዚህ ጋር ተዛምዶ ያላቸውና የሚገጥመውን አስገዳጅ ሁኔታ ለመቆጣጠር የሚያስችሉ ርምጃዎች ሊወሰዱ እንደሚችሉ ታምኖበት የተደነገገ ነበር ።

ሆኖም ከሕዝብ የቀረቡት አስተያየቶች የንዑስ አንቀጹን ይዘት ይበልጥ ግልጽ ማድረግ ጠቃሚ እንደሚሆን በማመልከታቸውና ኮሚሽኑም ለቀረቡት አመልካች ሐሳቦች ተገቢውን ግምት በመስጠቱ « የመንግሥት ምክር ቤት ብሔራዊ ሸንጐ በማይሰበሰብበት ጊዜ አስገዳጅ ሁኔታ ሲፈጠር ፣ የአስቸኳይ ጊዜ ሁኔታን ፣ ጦርነትን ወይም ሰላምን ሊያውጅ ይችላል ። » ይል የነበረው አንቀጽ ፹፫ ንዑስ አንቀጽ (፪) ፣

«የመንግሥት ምክር ቤት ብሔራዊ ሸንጐ በማይሰበሰብበት ጊዜ አስገዳጅ ሁኔታ ሲፈጠር ፣ የአስቸኳይ ጊዜ ሁኔታን ፣ ጦርነትን ፣ የጦር ጊዜ አስተዳደርን ፣ ክተትን ወይም ሰላምን ሊያውጅ ይችላል ። »

በሚል እንዲሻሻል ተደርጓል ።

ለሕዝብ ውይይት ቀርቦ በነበረው ረቂቅ ሰነድ ላይ በቀረበው አስተያየት መሠረት ማስተካከያ የተደረገበት ሌላው ጉዳይ በአንቀጽ ፹፬ ንዑስ አንቀጽ (፪) የተደነገገው ነው ። ከሕዝብ የቀረበው ጥያቄ ሲጠቃለል ኮሚሽነር መሆንና የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባል መሆን ሁልጊዜ የተያያዙ ጉዳዮች ናቸውን ? የሚል ይዘት ያለው ነው ። በሕዝብ የቀረበው ጥያቄ እስከአሁን በአብዮቱ ዓመታት ከነበረው ሁኔታ ጋር ሲታይና ወደፊትስ ይህ በምን መልክ ሊቀጥል ይችላል ? የሚለውን እንደገና ለማየት ሲሞከር የተገኘው ውጤት በንዑስ አንቀጹ ላይ ማሻሻያ ማድረግን የሚጠይቅ ሆኖ ተገኝቷል ።

በኮሚሽነር ወይም የኮሚሽነር ደረጃ ባላቸው ግለሰቦች የሚመሩ መሥሪያ ቤቶች በተለያዩ ምክንያቶች የሚቋቋሙበት ሁኔታ ይኖራል ። መሥሪያ ቤቱ ኮሚሽን መሆኑ ወይም መሥሪያ ቤቱን የሚመራው ግለሰብ ኮሚሽነር ወይም የኮሚሽነር ደረጃ ያለው መባሉ በራሱ የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባል መሆንን ያስከትላል ማለት አይደለም ። በዚህ ስያሜና ደረጃ ተቋቁመው የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባል ሳይሆኑ ተግባራቸውን ለማከናወንና ኃላፊነታቸውን በሚገባ ለመወጣት የሚችሉ ተቋሞች እንደሚኖሩ ስለሚታመን ከንዑስ አንቀጹ «ኮሚሽነሮችና» የሚለው ቃል እንዲወጣ ተወስኗል ።

ከኮሚሽነሮች መካከል በሥራቸው ጠባይ የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባል የሚሆኑት በዚሁ ንዑስ አንቀጽ «በሕግ በሚወሰነው መሠረት ሌሎች - - -»በሚለው ሐረግ ሊሸፈኑ የሚችሉ በመሆናቸው የቃሉ መውጣት ሊኖር የሚችለውን ችግር የሚያስወግድ ብቻ ሳይሆን በዚህ ደረጃ የሚቋቋሙ መሥሪያ ቤቶች ከሚቋቋሙበት ዓላማና ለእድገት ከሚያበረክቱት ድርሻ ጋር በተያያዘ አደረጃጀታቸው ለተለያዩ ሁኔታዎች ምቹ ሆኖ እንዲገኝ ለማድረግ የሚያስችል

በአብዮቱ ዓመታት አንዳንድ በብሔራዊ ደረጃ ኮሚቴዎች ሲቋቋሙ የቆዩ መሆናቸውን በማመልከት ከሪፑብሊኩ ምሥረታ በኋላ እንደነዚህ ዓይነት ኮሚቴዎች አይኖሩምን ? የሚኖሩ ከሆነ በማን ነው የሚቋቋሙት ? የሚል ይዘት ያላቸው ናቸው ። ጥያቄዎቹ በትክክል እንዳመለከቱት የተጠቀሰው ዓይነት ኮሚቴ በጊዜያዊ ወታደራዊ አስተዳደር ደርግ ሲቋቋምና ተግባሩን ሲያከናውን ቆይቷል ። ወደፊትም ተግባራዊ እንቅስቃሴ ይህን ዓይነት ጠባይ ያላቸውን አካላት ማቋቋም ሊጋብዝ እንደሚችል ግንዛቤ ተገኝቷል ። የነዚህ ዓይነት አካላት የሚቋቋሙ ከሆነ የማቋቋሙ ሥልጣን የብሔራዊ ሸንጐ መሆን እንደሚገባው በኮሚሽኑ ታምኖበታል ።

ስለዚህም « ብሔራዊ ኮሚቴዎች » የሚል ሐረግ እንዲገባ ሆኖ « የሚኒስትሮች ምክር ቤት፣ ሚኒስቴሮች ፣ ኮሚሽኖችና ባለሥልጣኖች ፣ » ይል የነበረው አንቀጽ ፷፫ ንዑስ አንቀጽ (፫) (ለ)

« የሚኒስትሮች ምክር ቤት ፣ ሚኒስቴሮች ፣ ብሔራዊ ኮሚቴዎች ፣ ኮሚሽኖችና ባለሥልጣኖች ፣ »

እንዲል ሆኖ ተስተካክሏል ።

በዚህ ላይ የተደረገው ማስተካከያ ተገቢ በሆነባቸው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጾች ላይ መንጸባረቅ የነበረበት በመሆኑም « የሚኒስቴሮችን ፣ የኮሚሽኖችንና በቀጥታ ለሚኒስትሮች ምክር ቤት ተጠሪ የሆኑትን ሌሎች የመንግሥት አስተዳደር አካላት ሥራ ይመራል ፣ ያስተባብራል ፤ » ይል በነበረው አንቀጽ ፺፬ ንዑስ አንቀጽ (፬) ላይ «ብሔራዊ ኮሚቴዎችን » የሚል ሐረግ እንዲገባ ሆኖ ፤

« የሚኒስቴሮችን ፣ የብሔራዊ ኮሚቴዎችን ፣ የኮሚሽኖችንና በቀጥታ ለሚኒስትሮች ምክር ቤት ተጠሪ የሆኑትን ሌሎች የመንግሥት አስተዳደር አካላት ሥራ ይመራል ፣ ያስተባብራል ፣ »

በሚል እንዲስተካከል ተደርጓል ።

በዚህ ክፍል ውስጥ ከሕዝብ በተገኘው አስተያየት ላይ በመመሥረት ሌላ ለውጥ የተደረገው በአንቀጽ ፷፩ ላይ ነው።በዚህ አንቀጽ ላይ የቀረበው አስተያየት ሲጠቃለል በንዑስ አንቀጽ(፩)እና (፬) የተጠቀሱት መርሖች በተግባር ሲተረጐሙ አፈጻጸም ላይ ችግር አይኖርምን?የሚል ይዘት ያላቸው ናቸው።ኮሚሽኑ ከዚህ ላይ በመመሥረት አንቀጹን እንደገና መርምሮታል።አንቀጽ ፷፩ ንዑስ አንቀጽ (፩) አራት ዋና ዋና የምርጫ መርሖችን በመደንገግ « የሕዝብን ብዛት መሠረት በማድረግ » የሚል ከአፈጻጸም ጋር የተያያዘ ሐረግ እንዲይዝ ተደርጐ ነበር ። ይህ ሐረግ ከምርጫ አፈጻጸም ጋር የተያያዘ እንደመሆኑ በንዑስ አንቀጽ (፬) ከተመለከተው ጋር በተዛመደ መንገድ በተግባር የሚገለጽ ነው ።

ስለሆነም ኮሚሽኑ ዋና ዋና የምርጫ መርሖችን በአንድ ንዑስ አንቀጽ ፣ ለአፈጻጸም በሚረዱ ሕጐች መሠረትነት በተግባር የሚተረጐሙ ከምርጫ ጋር የተያያዙ ጉዳዮችን ደግሞ በተለያዩ ንዑሳን አንቀጾች እንዲቀረጹ ቢደረግ አንቀጹ የሚያስተላልፈውን መልዕክት ይበልጥ ግልጽ ሊያደርገው እንደሚችል አምኖበታል ። በዚሁ መሠረት «የሕዝብን ብዛት መሠረት በማድረግ» የሚለው ሐረግ ከንዑስ አንቀጽ (፩) እንዲወጣ በማድረግ « የብሔራዊ ሸንጐ አባላት ምርጫ የሕዝብን ብዛት መሠረት በማድረግ ሁሉ አቀፍ ፣ እኩል ፣ ርቱዕና በምሥጢር ይሆናል ። » ይል የነበረው ፣

«የብሔራዊ ሸንጐ አባላት ምርጫ ሁሉ አቀፍ ፣ እኩል ፣ ርቱዕና በምሥጢር ይሆናል።»እንዲል ሆኖ ተስተካክሏል ።

በንዑስ አንቀጽ (፬) «የሕዝብን ብዛት መሠረት በማድረግ » የሚለውን አስተሳሰብ ራሱን ችሎ ፣

በንዑስ አንቀጽ እንዲቀረጽ በመወሰኑ ፣ «የብሔራዊ ሸንጐ አባላት ምርጫ የሕዝብን ብዛት መሠረት ያደርጋል ።»

የሚለው የአንቀጽ ፷፩ ንዑስ አንቀጽ (፬) ሆኖ እንዲገባ ተደርጓል ።

በዚሁ ምክንያት « በምርጫው ሂደት ብሔረሰቦች በብሔራዊ ሸንጐ መወከላቸው ይረጋገጣል ። » ይል የነበረው የቀድሞው ንዑስ አንቀጽ (፬) ንዑስ አንቀጽ (፫) ሆኗል ።

በሌሎችም ሕጎች የሚሰጧቸውን ተግባራት የማከናወን ኃላፊነት ያላቸው ናቸው ። ለአካላቱ የጋራ የሆነው ተግባር በሕገ መንግሥቱ ላይ በመመሥረት የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ በቀየሰው የእድገት ጎዳና በተፋጠነ እንዲራመድ ማድረግ ነው ። ይህ የጋራ ተግባር እንደሁኔታው በጋራና በግል ኃላፊነት ላይ በመመሥረት መከናወን የሚኖርበት በመሆኑ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ያላቸውን የዓላማ አንድነት መሠረት በማድረግ ሥራዎች ተቀናጅተው ሊራመዱ በሚችሉበት እንደ መልክ የሥራ ድልድል አድርጓል ። ይህም የታቀደውን ግብ ለመምታት አመቺ ሁኔታን እንደሚፈጥር ይታመናል ።

ሪፐብሊኩ በአስተዳደር አካባቢዎችና በራስ ገዝ አካባቢዎች እንዲዋቀር መሆኑና ብሔራዊ ሸንጎና እርሱም በማይሰበሰብበት ጊዜ ተግባሩን በሚያከናውኑለት አካላት አመራር ሥር ሆነው የአካባቢዎችን ተግባራት የሚመሩ ሸንጎዎች እንዲኖሩ መደረጉ ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ ሁለንተናዊ የተፋጠነ እድገት ከፍተኛ ድርሻ እንደሚያበረክቱ ታምኖበት ነው ። የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ መደባዊ አንድነቱን ይበልጥ እያጠናከረ መሄድ የሚችልበት ሁኔታ የተፈጠረ በመሆኑም ይህ ለተፋጠነ እድገት የተሰጠው ትኩረት አስተማማኝ ውጤት የሚያስገኝ ይሆናል ። በእድገታቸው በዝቅተኛ ደረጃ ላይ ለሚገኙት ብሔረሰቦች የተለየ ትኩረት መስጠት ያለበት ስለመሆኑና የአካባቢ የራስ በራስ አስተዳደር ተግባራዊ ስለሚሆንበት ሁኔታ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መደንገጉ ለሚጠበቀው ውጤት መገኘት ተጨማሪ ዋስትና እንደሚሆን ጥርጥር የለውም ።

ከላይ በምሳሌነት ከተጠቀሱት ለመመልከት እንደሚቻለው አብዛኛዎቹ በክፍሉ አንቀጾችና ንዑስ አንቀጾች ላይ የተነሱት ጥያቄዎችና አስተያየቶች ግልጽ የሆነ አመለካከት እንዲኖር ፣ ወይም ከሪፐብሊኩ ምሥረታ በኋላ ለሚጠብቀን የግንባታ ትግል የሚፈለገውን የመንግሥት አወቃቀር ይዘት በሚገባ ለመገንዘብ ከመፈለግ የቀረቡ ናቸው ። ስለሆነም በውይይቱ ወቅት በየመድረኩ ተሰማርተው በነበሩ የኮሚሽኑ ተወካዮች በተሰጡ ማብራሪያዎች እንደዚሁም በሕዝብ መገናኛዎች በተሰጡ መግለጫዎች ተገቢ መልስ ተሰጥቷቸዋል ። በተጨማሪ ከሕገ መንግሥቱ የማስተማሪያነት ጠባይ አኳያ ተግባራዊ እንቅስቃሴ በሚያሳየው ሁኔታ በመታገዝ የበለጠ ግንዛቤ የማግኘቱ ጉዳይ የሚቀጥል ይሆናል ።

ከላይ የተመለከቱት ጉዳዮች ሁሉ በሕገ መንግሥቱ ላይ ተመሥርተው በሚወጡ አስፈጻሚ ሕጎች ዝርዝር ይዘታቸው ይበልጥ ግልጽ ይደረጋል ። ስለ ሪፐብሊኩ ምክትል ፕሬዚዳንትም ሕገ መንግሥቱ ከደነገጋቸው ጉዳዮች በተጨማሪ በዝርዝር ሕጎች የሚሸፈኑ በርካታ ጉዳዮች ይኖራሉ ። ስለ ቀበሌ ፍርድ ሸንጎዎች ፣ ስለሌሎች ፍርድ ቤቶችና ስለ መሳሰሉት አካላት ሥልጣንና ተግባር እንዲሁም ስለ አሠራራቸው ሕገ መንግሥቱን መሠረት አድርገው በሚወጡ ሌሎች ሕጎች ሲደነገጉ የሕገ መንግሥቱ ይዘት በተሟላ ሁኔታ ግልጽ ሊሆን እንደሚችል ይታመናል ።

በዚህ ክፍል ውስጥ ሕዝቡ ባነሳቸው አስተያየቶችና ጥያቄዎች ላይ በመመሥረት ማስተካከያዎች ቢደረግባቸው ለረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ይዘት መበልጸግም ሆነ ለሚያስተላልፈው መልእክት ጥራት ማግኘት ይጠቅማሉ ተብሎ በኮሚሽኑ በታመነባቸው አንቀጽ ፳፫ (የቀድሞው አንቀጽ ፳፬) ንዑስ አንቀጽ (፫) (ለ) ፣ አንቀጽ ፳፭ (የቀድሞው አንቀጽ ፳፮)፣ አንቀጽ ፴፫ (የቀድሞው አንቀጽ ፴፬) ንዑስ አንቀጽ (፱) ፣ አንቀጽ ፴፱ (የቀድሞው አንቀጽ ፵)፣ እንቀጽ ፵፪ (የቀድሞው አንቀጽ ፵፫)ንዑስ አንቀጽ (፱) እና (፳) (የቀድሞው ንዑስ አንቀጽ (፯) ፣ አንቀጽ ፵፫ (የቀድሞው አንቀጽ ፵፬) ንዑስ አንቀጽ (፩) እና (፱) አንቀጽ ፵፮ ( የቀድሞው አንቀጽ ፵፳) ፣ አንቀጽ ፩፻፩ እና አንቀጽ ፩፻፭ ( የቀድሞው አንቀጽ ፩፻፪ እና አንቀጽ ፩፻፮) ላይ ማስተካከያዎች ተደርገዋል ።

ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ለሕዝብ ውይይት በቀረበበት ጊዜ በአንቀጽ ፳፫ ንዑስ አንቀጽ ፫ (ለ) መሠረት ብሔራዊ ሸንጎ የሚያቋቁማቸው አካላት የሚኒስትሮች ምክር ቤት ፣ ሚኒስቴሮች ኮሚሽኖችና ባለሥልጣኖች እንደሚሆኑ ተደንግጎ ነበር ። በውይይቱ ወቅት የቀረቡት ጥያቄዎች

በዚህ ክፍል ውስጥ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ከፍተኛ የውክልና የሥልጣን አካል ስለሆነው ስለብሔራዊ ሸንጎ ፤ የሸንጎው ቋሚ አካል ስለሆነው ስለመንግሥት ምክር ቤት ፤ ስለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ፤ ስለሚኒስትሮች ምክር ቤት ፤ ስለአካባቢዎች የሥልጣንና የአስተዳደር አካላት ስለዳኝነት እና ስለዐቃቤ ሕግ መሥሪያ ቤት ተደንግጓል ።

በሕገ መንግሥቱ በግልጽ እንደተመለከተው የብሔራዊ ሸንጎ አባላት በቀጥታ በሕዝብ የሚመረጡ ናቸው ። ለተመራጭነት የሚያበቁ መሠረታዊ መመዘኛዎች እንደተጠበቁ ሆነው በኢትዮጵያውያን ላይ ምንም ዓይነት ልዩነት ሳይደረግ የመምረጥና የመመረጥ መብት በሕገ መንግሥቱ ተደንግጓል ። ዕጩዎች በሕገ መንግሥቱ በተመለከቱ አካላት የሚጠቆሙ ቢሆንም ለተመራጭነት ብቁ ሆኖ መገኘት ከዜግነት የሚመነጭ መብት እንጂ ድርጅቶችን ወይም ተቋሞችን በመወከል የሚመሠረት አይደለም ። ሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነቱን ተግባራዊ የሚያደርገውም በዚህ መልክ የሚመርጣቸው ወኪሎች በአባልነት በሚኖሩበት በብሔራዊ ሸንጎ አማካኝነት ነው ። ይህ ክፍል የሚሸፍናቸው ከላይ የተጠቀሱት ሌሎች የመንግሥቱ አካላት ሥልጣን ምንጭ የሚሆነውም ብሔራዊ ሸንጎ ነው ።

ለነዚህም አካላት ሕገ መንግሥቱ የሚደነግጋቸው ልዩ ልዩ ጉዳዮች መኖራቸው እንደተጠበቀ ሆኖ በእነዚህ ላይ በመመሥረት በሚወጡ ዝርዝር ሕጎች ተጨማሪ ተግባርና ኃላፊነታቸው የሚገለጽ ይሆናል ። በሕገ መንግሥቱ ያልተጠቀሱ ነገር ግን ለሪፑብሊኩ ተግባራት በተሟላ መራመድ አስፈላጊ የሚሆኑ ሌሎች አካላት እንዳስፈላጊነቱ በሌሎች ሕጎች ሊመሠረቱና ተግባርና ኃላፊነታቸው ሊደነገግ የሚችል መሆኑም ግልጽ ነው ። አንዳንድ ጉዳዮች ለዝርዝር ሕጎች መተዋቸውም ሕገ መንግሥቱ ካለው ጥቅል የመሆን ባሕርይ የሚመነጭ ነው ።

የኢትዮጵያ ሕዝብ የመንግሥት አካላትን በሚመለከቱ አንቀጾች ላይ ውይይት ባካሄደበት ወቅት እንደሌሎቹ የሕገ መንግሥቱ ክፍሎች ሁሉ ልዩ ልዩ ጥያቄዎችንና አስተያየቶችን አቅርቧል ። ከነዚህም ዋና ዋናዎቹን ለማመልከት ፡—

—የሪፑብሊኩ አወቃቀር ተግባራዊ ሲሆን ምን መልክ ይኖረዋል ?

—የሃይማኖት ተቋሞች ለብሔራዊ ሸንጎ ዕጩዎችን እንዲጠቁሙና ተቋሞቹም እንዲወከሉ የሚወስን አንቀጽ ሊገባ አይችልምን ?

—በመንግሥት ምክር ቤትና በሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት መካከል ያለው የሥልጣን ድርሻ ይጣጣማልን ?

—የሪፑብሊኩ ምክትል ፕሬዚዳንት ሥልጣንና ተግባር በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ቢገለጥ ፤

—የቀበሌ የፍርድ ሸንጎዎችና ሌሎች ፍርድ ቤቶች በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ለምን አይጠቀሱም ?

—ዐቃብያነ ሕግ በጠቅላይ ዐቃቤ ሕግ የሚሾሙት የሕግ አንድ ወጥ አፈጻጸምን ለማረጋገጥ ካለው ኃላፊነት የሚመነጭ ነው ወይስ ሌላ ምክንያት አለው ?

የሚሉና የመሳሰሉ ናቸው ።

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሁሉም ብሔረሰቦች በእኩልነት የሚኖሩበት አሐዳዊ መንግሥት ስለመሆኑና በአስተዳደር አካባቢዎችና በራስ ገዝ አካባቢዎች የሚዋቀር መንግሥት ስለመሆኑ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ልዩ ልዩ አንቀጾች ተደንግጓል ። በዚህ መልክ በሚዋቀረው መንግሥት የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ከፍተኛ የሥልጣን ባለቤትነት መግለጫ ከሆነው ከብሔራዊ ሸንጎ ጀምሮ እስከ መሠረታዊ የአስተዳደር አሐድ ድረስ በምርጫ የሚቋቋሙ የሥልጣን አካላት እንደሚኖሩም በተለያዩ አንቀጾች ተመልክቷል ።

በብሔራዊ ሸንጎ ሥር ሆነው ተግባራቸውን የሚያከናውኑ የአካባቢ የሥልጣን አካላት የመኖራቸው ጉዳይ እንደተጠበቀ ሆኖ በማዕከል ደረጃ ሸንጎው በሕገ መንግሥቱ ላይ በመመሥረት በሥልጣን አካልነት የሚመሠርታቸው የመንግሥት ምክር ቤትና የሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት እንደሚኖሩ በግልጽ ተመልክቷል ። እነዚህ የሥልጣን አካላት ሸንጎው በሚሰበሰብበት ጊዜ ከሚኖሯቸው ተግባራት በተጨማሪ ሸንጎው ስብሰባ ላይ በማይሆንበት ጊዜ በሕገ መንግሥቱና

« ጋብቻ አካለ መጠን በደረሱ በአንድ ሴትና በአንድ ወንድ መካከል በፈቃደኝነት ላይ የተመሠረተ ነው ። ባልና ሚስት በቤተሰብ ግንኙነታቸው እኩል መብት አላቸው ። ጋብቻ የመንግሥት ጥበቃ ይደረግለታል ። »

እንዲል ሆኖ ተሻሽሏል ።

የዜጎች መሠረታዊ ነፃነቶች ፡ መብቶችና ግዴታዎች በሚለው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ክፍል ውስጥ ከሕዝብ ውይይት በቀረቡ አስተያየቶች ላይ በመመሥረት ሌሎች ማሻሻያዎች የተደረጉት በአንቀጽ ፴፰ (የቀድሞው አንቀጽ ፴፮) ንዑስ አንቀጽ (፩) እና በአንቀጽ ፴፫ (የቀድሞው አንቀጽ ፴፪) ንዑስ አንቀጽ (፫) ላይ ነው ። በነዚህ አንቀጾች ላይ ከሕዝብ የቀረቡት አስተያየቶች አብዛኞዎቹ በተለይ አንቀጽ ፴፬ ንዑስ አንቀጽ (፩) ለወንጀል ድርጊቶች መስፋፋት መንገድ እንዳይከፍት ይሻሻል በሚለው አስተሳሰብ ላይ የተመሠረቱ ናቸው ። በአንቀጽ ፳፫ (የቀድሞው አንቀጽ ፳፪) ንዑስ አንቀጽ (፩) ላይ የቀረቡ አስተያየቶችም ከዚሁ ጋር የሚመሳሰሉ ናቸው ።* በዚሁ አስተሳሰብ ላይ የተመሠረቱ ጥያቄዎች በአብዛኛው ግንዛቤን የሚመለከቱ ሆነው በመገናኛው በተሰጡት ገለጻዎችና ማብራሪያዎች ተገቢውን መልስ እንዲያገኙ ተደርጓል ።

ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ አንቀጾቹ ለሚያስተላልፏቸው መልዕክቶች ይበልጥ ጥራት መስጠት የሚያስገኘው ጠቀሜታ ጉልህ መሆኑ በኮሚሽኑ ስለታመነበት በአንቀጽ ፴፬ ንዑስ አንቀጽ (፩) እና በአንቀጽ ፳፫ ንዑስ አንቀጽ (፩) «ካልተያዘ» ይል የነበረው «ካልተገኘ» በሚለው ፤ «በቁጥጥር ሥር አይውልም» ይል የነበረው «አይያዝም» በሚለው ተተክቶ « ማንኛውም ሰው ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተያዘ ወይም በፅሑፍ ሕግ ትዕዛዝ ወይም በፍርድ ቤት ውሳኔ ካልሆነ ወይም ሕግ ከሚደነግገው በስተቀር በቁጥጥር ሥር አይውልም ። » ይል የነበረው አንቀጽ ፴፬ ንዑስ አንቀጽ (፩) ፡

«ማንኛውም ሰው ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተገኘ ወይም በፅሑፍ ሕግ ትዕዛዝ ወይም በፍርድ ቤት ውሳኔ ካልሆነ ወይም ሕግ ከሚደነግገው በስተቀር አይያዝም ። »

እንዲል ሆኖ ፤ « አንድ የሕዝብ እንደራሴ ከባድ ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተያዘ በስተቀር ያለ ሸንጎው ወይም ሸንጎው ባልተሰበሰበበት ጊዜ ያለመንግሥት ምክር ቤት ፈቃድ በቁጥጥር ሥር አይውልም ፤ በወንጀልም አይከሰስም ። » ይል የነበረው አንቀጽ ፳፫ ንዑስ አንቀጽ (፩) ደግሞ ፤

« አንድ የሕዝብ እንደራሴ ከባድ ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተገኘ በስተቀር ያለ ብሔራዊ ሸንጎ ወይም ሸንጎው ባልተሰበሰበበት ጊዜ ያለ መንግሥት ምክር ቤት ፈቃድ አይያዝም ፤ በወንጀልም አይከሰስም ። »

እንዲል ሆኖ ተስተካክሏል ። እንዲሁም በአንቀጽ ፴፬ ንዑስ አንቀጽ (፪) «በቁጥጥር ሥር የዋለ» ይል የነበረው « ማንኛውም የተያዘ » በሚለው ተተክቶ ፤

«ማንኛውም የተያዘ ሰው በ፵፰ ሰዓት ውስጥ ወደ ፍርድ ቤት መቅረብ አለበት ፤ ሆኖም ይህ ጊዜ ወደ አቅራቢያው ፍርድ ቤት ለመድረስ የሚያስፈልገውን ጊዜ አይጨምርም ። »

እንዲል ሆኖ ተስተካክሏል ።

አንቀጽ ፴፫ (የቀድሞው አንቀጽ ፴፪) ንዑስ አንቀጽ (፫) የሚያስተላልፈውን መልዕክት ይበልጥ ግልጽ ማድረግ አስፈላጊ መሆኑ በኮሚሽኑ ስለታመነበትም « በከፍተኛ ወንጀል » ይል የነ

---

* አንቀጽ ፳፫ በዚህ ክፍል ውስጥ የማይገኝ ቢሆንም የተነሱት ጉዳዮች ተመሳሳይነት ስላላቸው በአንቀጹ ላይ የተነሱ ጥያቄ ዎችና የተደረጉ ለውጦች በዚህ ክፍል እንዲሸፈኑ ተደርጓል ።

ውም በዚሁ የእኩልነት ጽንሰ ሐሳብ ላይ በመመሥረት ነው ። ይህ መሠረተ ሐሳብ እንደተ ጠበቀ ሆኖ «ሴቶች ከወንዶች ጋር» የሚለው ሐረግ አሁንም ሴቶች የበታች ናቸው የሚል ስሜት የሚፈጥር ስለሚመስል ይስተካከል የሚል አስተያየት የቀረበ በመሆኑ ይህን ንዑስ አንቀጽ እንደገና መመልከት አስፈላጊ ሆኗል ። በዚህም መሠረት ኮሚሽኑ ትክክለኛው መል ዕክት መተላለፍ እንዲችል «. . . ሴቶች ከወንዶች ጋር . . .» ይል የነበረው «. . . ሴቶችና ወንዶች . . .» በሚለው እንዲስተካከል በመወሰኑ አንቀጽ ፴፮ ንዑስ አንቀጽ (፩)፡*

> «በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሴቶችና ወንዶች እኩል መብት አላቸው ።»

እንዲል ሆኖ ተሻሽሏል ።

ሌላው ኮሚሽኑ የተለየ ትኩረት የሰጠውና ለረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መስተካከል የወሰ ደው በአንቀጽ ፴፯ (የቀድሞው አንቀጽ ፴፰) ንዑስ አንቀጽ (፩) ላይ የቀረቡ የማሻሻያ አስተያየቶችን ነው ። ይህ ንዑስ አንቀጽ እንዳለ ይቆይ የሚሉ አስተያየቶች ቀርበው የነበረ ቢሆንም በንዑስ አንቀጹ ላይ ከቀረቡት አስተያየቶች አብዛኛዎቹ «በጋብቻ ላይ ጋብቻ የተከለ ከለ ነው» የሚለው የንዑስ አንቀጹ ክፍል የተለያዩ እምነቶችንና ባህሎችን የሚጻረር ስለሚመ ስል ይሻሻል በሚለው አስተሳሰብ ላይ የተመሠረቱ ናቸው ።

ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ የደነገጋቸው ጽንሰ ሐሳቦች የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ በአብ ዮቱ ዓመታት የተቀዳጃቸውን ድሎችና የአብዮቱን የወደፊት አቅጣጫ በሚገባ መሠረት ያደረጉ ናቸው ። ከነዚህም ዋነኛው የዜጎች እኩልነት መረጋገጥ ነው ። ይህ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በመደንገጉ ብቻ የተገለጸ ሳይሆን በአብዮቱ ዓመታት በልዩ ልዩ መልኩ እየዳበረ የመጣ ነው ። በሕገ መንግሥቱም ላይ በሰፈሩ ድንጋጌዎች ተለይቶ በተጠናከረ መልክ መቀ ጠል ያለበት መሆኑም ከምንከተለው ፖሊሲ ጋር የሚጣጣም ነው ። የዜጎችን እኩልነት የሚያናጋ ሁኔታ መቀበል የአብዮቱን ድሎችና ሂደቱን ከጥያቄ ውስጥ የሚያስገባ ይሆናል ። ስለ ዚህም የዜጎች የእኩልነት መብት በረቂቁ ላይ በተጠቀሰው መንፈስ የሚረጋገጥበት ሁኔታ መደንገጉ አማራጭ የማይገኝለት ነው ። ስለሆነም ኮሚሽኑ ይህ መሠረታዊ ሐሣብ ሳይዛነፍ «በጋብቻ ላይ ጋብቻ የተከለከለ ነው» የሚለው የንዑስ አንቀጹ ክፍል እንደገና ይታይ የሚ ለውን የሕዝቡን አስተያየት በጥሞና መመልከት አስፈላጊ ሆኖ አግኝቶታል ።

በመሠረቱ በንዑስ አንቀጹ ላይ የተጠቀሰው ይህ ሐረግ የሚጨምረው ነገር ቢኖር በጋብቻ ላይ ጋብቻ የፈጸመ «በወንጀል ይከሰሳል፣ ይቀጣል» የሚለውን አስተሳሰብ ነው ። የዚህ አስተሳሰብ ከሕገ መንግሥቱ መውጣት ደግሞ ከአንድ በላይ ጋብቻን መንግሥት ይደግ ፋል ወደሚለው አስተሳሰብ የሚያመራ ሳይሆን በፖለቲካዊ፣ በኢኮኖሚያዊ፣ በማኅበራዊና በባህ ላዊ ዕድገት ላይ ለሚደረስበት ለውጥ ተገቢውን ሥፍራ የሚሰጥ መሆኑን የሚያመለክት ነው ።

ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ለሕዝብ ውይይት ከመቅረቡ አስቀድሞ ከአንድ በላይ በተፈጸሙ ጋብቻዎች የተመሠረቱ በርካታ ቤተሰቦች በመኖራቸውና በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ የሰፈ ረው እነዚህን ሁሉ ሥጋት ውስጥ የጨመረ ጉዳይ ሆኖ ታይቷል ። ረቂቅ ሕገ መንግ ሥቱ የተነሳበት የሴቶችን እኩልነት ጽንሰ ሐሣብ (በቤተሰብ ውስጥ ጭምር) የሚያዛንፍ ውጤት እስካላስከተለ ድረስ ሐረጉ ቢወጣ የተሻለ እንደሚሆን በኮሚሽኑ በመወሰኑ እንዲ ወጣ ተደርጓል ። በዚሁ መሠረት «ጋብቻ ለአካለ መጠን በደረሱ በአንድ ሴትና በአንድ ወንድ መካከል በፈቃደኝነት ላይ የተመሠረተ ነው ። በጋብቻ ላይ ጋብቻ የተከለከለ ነው ። ባልና ሚስት በቤተሰብ ግንኙነታቸው እኩል መብት አላቸው ። ጋብቻ የመንግሥት ጥበቃ ይደረግለ ታል ።» ይል የነበረው አንቀጽ ፴፯ ንዑስ አንቀጽ (፩)፡

---

* አንቀጾቹ ከዚህ በኋላ በተናጠል ሲጠቀሱ ለውሳኔ ሕዝብ በቀረበው ረቂቅ ላይ በያዙት ቁጥር መሠረት ይሆናል ።

መንገድ ስለሚከፍት ቢስተካከል ፤

—የአምልኮ ቦታዎች የተከበሩ መሆናቸው በግልጽ ቢደነገግ ፤

—እናት አገሩን ከዳ የሚባለው ምን ያደረገ ኢትዮጵያዊ ነው ?

—በዚህ ክፍል የተደነገጉት ነፃነቶችና መብቶች ለፀረ አብዮተኞች መጠቀሚያ እንዳ ይሆኑ ጥንቃቄ ይደረግ ፤

የሚሉና የመሳሰሉት ናቸው ።

በተለያዩ አጋጣሚዎች ለማመልከት እንደተሞከረው ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መሠረታዊ የሆነውን የዜጐችን እኩልነት መነሻ በማድረግ የተቀረጸ ነው ። ይህ የእኩልነት መብት ሁለንተናዊ በሆነ መልኩ ተግባራዊ መሆን ያለበት ስለመሆኑ ሕገ መንግሥታዊ ማረጋገጫ እንዲሰጥ ሆኖ የተዘጋጀ ነው ። ዜጐች በኢትዮጵያዊነታቸው ሊያገኙት የሚገባውን ጥቅም ያለልዩነትና በተሟላ መልክ እንዲያገኙ ለማስቻል መሠረት የሚጥል ነው ። ከዜግነት የሚመነጩ ግዴታዎችም በእኩልነት ተፈጻሚ መሆን እንዳለባቸው የሚያመለክት ነው ። ስለዜግነት ፣ ስለሃይማኖቶች እኩልነት ፣ ስለ ልጆች እኩልነትና ሌሎችንም መሰል ጉዳዮች የሚደነግጉት የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጾች ይህን መሠረታዊ አስተሳሰብ በማጤን የተቀረጹ ናቸው ።

ከላይ ከተጠቀሱት ጥያቄዎች መካከል አብዛኞዎቹ ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ላይ ተመሥርተው በሚወጡ ዝርዝር ሕጐች ቀጥተኛ መልስ የሚያገኙ ናቸው ። የዜግነት ሕግ ፣ የቤተሰብ ሕግ ፣ የወንጀል ሕግ ፣ ሌሎችም ከጥያቄዎቹ ጋር ቀጥተኛ ግንኙነት የሚኖራቸው ሕጐች በሚወጡበት ጊዜ እያንዳንዱ ጉዳይ በዝርዝር የሚሸፈንበት ሁኔታ ይኖራል ። ስለዚህም ከወላጆቹ አንዱ የውጭ አገር ዜጋ የሆነ ልጅ ዜግነቱን ስለሚመርጥበት ሁኔታ ፣ የልጆች እኩልነት ማረጋገጫ ተግባራዊ መግለጫዎች ፣ የአምልኮ ቦታዎች የሚከበሩበት ሁኔታ ፣ አገርን የመክዳት ወንጀል የሚከሰትባቸው ድርጊቶችና የመሳሰሉት ሁሉ የሚገለጹ ናቸው ። ሪፑብሊኩ ሕገ መንግሥቱንና ሌሎችንም የሚያወጣቸውን ሕጐች የማስፈጸም ሥልጣን የሚኖረው በመሆኑም ወንጀልን ለመከላከልም ሆነ የዜጐችን መብቶች ለማስከበር በጠቅላላውም ሥርዓቱን ለመጠበቅ የሚችል ይሆናል ።

ለረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ልዩ ልዩ ክፍሎች እንደተደረገው ሁሉ በዚህም ክፍል ላይ ለተነሱ ግንዛቤን ለሚመለከቱ ጉዳዮች በውይይት መድረኮችና በሕዝብ መገናኛዎች ተገቢው ማብራሪያና ገለጻ ሲሰጥ ቆይቷል ። በዚህ መልክ ሕዝቡ በዝርዝር እንዲጨብጣቸው ለማድረግ ካገዙ ጥያቄዎችና አስተያየቶች ሌላ የውይይቱ ሂደት በዚህም ክፍል ውስጥ የተደነገጉትን ጉዳዮች ለማሻሻልና ለማስተካከል ያስቻሉ ሐሳቦችን አስገኝቷል ። ከነዚህም ሐሳቦችና አስተያየቶች ዋና ዋናዎቹ ፡—

—የሴቶችና የወንዶች እኩልነት ይበልጥ ጠንከር ብሎ ይገለጽ ፤

—ነጠላ ጋብቻ ብቻ የተፈቀደ መሆኑን መደንገግ በአንዳንድ ሃይማኖቶችና ባህሎች ላይ ተጽእኖ ስለሚያደርግ ቢሻሻል ፤

የሚሉ ይገኙባቸዋል ።

የሴቶችና የወንዶች እኩልነት የተረጋገጠ ስለመሆኑ ጠንከር ብሎ ይገለጽ የሚለው ከብዙ ኢትዮጵያውያን ሴቶችና ወንዶች የተነሳው ጥያቄ በኮሚሽኑ በጥሞና ከተመረመሩ ጉዳዮች አንዱ ነው ።

በመሠረቱ ለሕዝብ ውይይት የቀረበው ረቂቅ ሕገ መንግሥት ነፃነቶችን ፣ መብቶችንና ግዴታዎችን በተመለከተ በዜጐች መካከል ምንም ዓይነት ልዩነት እንደማይደረግ ማለትም ዜጐች ሁሉ እኩል መሆናቸውን የሚደነግግ ነው ። ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በዜጐች መካከል በጾታ ላይ የተመሠረተ ልዩነት የማይደረግ መሆኑን በአንቀጽ ፴፯ (የቀድሞው አንቀጽ ፴፮) ንዑስ አንቀጽ (፩) ላይ « . . . ሴቶች ከወንዶች ጋር እኩል መብት አላቸው ። » በማለት የደነገገ

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ጽኑ የመከላከያ ኃይል ይኖረዋል ።

«፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የመከላከያ ኃይል ለአገር አንድነትና

፪. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የመከላከያ ኃይል ለአገር አንድነትና ለሥርቶ አደሩ ሕዝብ የበላይነት ፡ ለሰላምና ለሶሻሊዝም የቆመና የሚታገል የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ሠራዊት ነው ። »

በማለ እንዲቀረጹ ተደርጓል ። *

## 3.3 ክፍል ሁለት—ዜግነት ፡ ነፃነቶች ፡ መብቶችና ግዴታዎችን በሚመለከት

ይህ ክፍል የኢትዮጵያ ዜጋ መሆን ከፍተኛ ክብርና የፖለቲካ ትርጉም ያለው ፡ ሕገ መንግሥቱና በሕገ መንግሥቱ ላይ ተመሥርተው ነሚወጡ ሕጎች በሚሰጡት መብት ተጠቃሚና የሚጥሉትን ግዴታ ፈጻሚ የሚሆነው ማን እንደሆነ በመመለስ የዜጎችን ሕገ መንግሥታዊ ነፃነቶች ፡ መብቶችና ግዴታዎች የሚደነግግ ነው ።

በዚህ ክፍል ውስጥ የተደነገጉት ነፃነቶችና መብቶች የኢትዮጵያ ሕዝብ ለዓመታት ሲታገልላቸው የነበሩ ፡ በከፍተኛ መስዋዕትነት የተገኙና ከአብዮታችን ድል ማድረግ በኋላም በየደረጃው በተወሰዱ ርምጃዎች ተጨባጭነታቸው ከጊዜ ወደ ጊዜ እየተረጋገጠ የመጡ ናቸው ። በምንገኝበት የእድገት ደረጃ ላይ ተመሥርተው የተቀረጹና ለሶሻሊስት ሥርዓት ግንባታ መሠረት በምንጥልባቸው የወደፊቱ የትግል ዓመታትም በሕገ መንግሥቱ ተጨማሪ መሣሪያነት ይበልጥ እየዳበሩ የሚሄዱ ናቸው። እነዚህ መብቶችና ነፃነቶች የኢትዮጵያ ሕዝብ ባለፉት የአብዮት ዓመታት ተግባራዊ ሲያደርጋቸው የቆዩ ናቸው ። በኢሕዲሪም ሠርቶ አደሩ ሕዝብ ቀጥተኛ የሥልጣን ባለቤት በመሆን በሪፑብሊኩ አካላት አማካኝነት ይበልጥ በተሟላ መልካቸው ተግባራዊ የሚያደርጋቸው ይሆናሉ ። በዚህ ክፍል ውስጥ የተደነገጉት ጠቅለል ባለ መልክ ሲታዩ ቡድናዊ መብቶች፡ ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ መብቶች ፡ ፖለቲካዊ መብቶች ፡ ፍትሕ ነክ መብቶች ፡ ነፃነቶችና ግዴታዎች ተብለው ሊያዙ የሚችሉ ናቸው ።

በዚህ የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ክፍል የታቀፉትን ጉዳዮች በአብዮቱ መሠረታዊ ዓላማና ግኝቶች ላይ የተመሠረቱና ከሕዝቡ የዕለት ተዕለት ሕይወት ጋር የተያያዙ ጉዳዮችን የሚመለከቱ ናቸው ። መንግሥትና ኅብረተሰብ ከዜጎች ጋር እንዲሁም ዜጎች እርስ በርሳቸው ያላቸውን ግንኙነት የሚደነግጉ አንቀጾችን የያዘ ክፍል በመሆኑም በውይይቱ ወቅት አያሌ ጥያቄዎችን ያስነሳና ከሌሎች ክፍሎች በበለጠ አስተያየቶች የቀረቡበት ሊሆን ችሏል ።

በዚህ ክፍል ላይ የተነሱ ጥያቄዎችና የቀረቡት አስተያየቶች በአብዛኛው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ይዘት በይበልጥ ለመረዳት ወይም መልዕክቱን በትክክል ለመጨበጥ ባለ ፍላጎት ላይ የተመሠረቱ ሲሆኑ ጥቂቶቹ መሠረታዊ የዜጎች የእኩልነት መብትን ከጥያቄ ያስገቡ ፡ በለተያዩ እምነቶችና ባህሎች ላይ የተመሠረቱ ነበሩ ። በዚህ ክፍል ውስጥ የተነሱትን ጥያቄዎች በኅብረተሰባችን ውስጥ የሚገኙ ልዩ ልዩ ማኅበራዊ ክፍሎች በአብዮታችን ሂደት የተቀዳጇናቸውን ድሎች እንዴት እንደሚረድዋቸው ፡ የወደፊቱን ጉዟችንን እንዴት እንደሚመለከቱና የነርሱ ፍላጎት ይበልጥ እንዴት መንጸባረቅ እንዳለበት ለማመልከት የቻሉ ጥያቄዎችና አስተያየቶች ናቸው ።

ከተነሱት ጥያቄዎችና ከቀረቡት አስተያየቶች ዋና ዋናዎቹ ፡-

—ከወላጆቹ አንዱ የውጭ አገር ዜጋ የሆነ ሰው ዜግነቱን ለመምረጥ ይችላልን ?

—ከጋብቻ ውጭ ለሚወለዱ ልጆች እኩል መብት መስጠት በሕጋዊ ጋብቻ ላይ ለተመሠረተ ቤተሰብ ጠንቅ ስለሚሆን ቢስተካከል !

—«ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተያዘ በስተቀር» የሚለው ሐረግ ለወንጀል መስፋፋት

---

* ሁለት አንቀጾች በአንድ አንቀጽ እንዲጠቃለሉ በመደረጉ ለሕዝብ ውይይት ቀርቦ በነበረው ረቂቅ ላይ 120 የነበሩት የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ አንቀጾች ለውሳኔ ሕዝብ በቀረበው ላይ 119 ሆነዋል ። ስለዚህም ከአንቀጽ 25 በኋላ የነበሩት አንቀጾች በአንድ ቁጥር እየተቀነሱ ተሸጋሽገዋል ።

ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በተለያየ መልክ የሚያደርጋቸው እንቅስቃሴዎች ጤናማ አእምሮና አካል የሚሹ መሆናቸው ግልጽ ነው ። ጤናማ አእምሮና አካል ማግኘት ከሚያስችሉ ጉዳዮች አንዱ አካል ማሠልጠንና ስፖርትን ማዘውተር እንደሆነም ይታወቃል ። ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ለዚህ ጉዳይ ተገቢውን ትኩረት ሰጥቶ በአንቀጽ ፲፱ ላይ ደንግጎት የነበረ ቢሆንም ይበልጥ ግልጽ ሆኖ መውጣት ያለበት መሆኑ በሕዝብ አስተያየቶች ስለ ተሰጠበትና የሕገ መንግሥት አርቃቂ ኮሚሽኑም ለእነዚህ አስተያየቶች ክብደት በመስጠት ስፖርትን የሚመለከት ራሱን የቻለ ንዑስ አንቀጽ እንዲገባ በመወሰኑ ፣

« መንግሥትና ኅብረተሰብ ዜጎች የአካል ማሰልጠን እንቅስቃሴንና ስፖርትን እንዲያዘወትሩ አስፈላጊውን ድጋፍ ይሰጣሉ ። »

የሚለው የአንቀጽ ፲፱ ንዑስ (፪) ሆኖ እንዲገባ ተደርጓል ።

በዚህ ምዕራፍ ውስጥ በውይይቱ ወቅት ተነስተው ለረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መዳበር ምክንያት የሆኑ ሌሎች ጉዳዮች ባህልና የታሪክ ቅርሶችን በተመለከተ በአንቀጽ ፳፫ በተደነገገው ላይ የተመሠረቱ ናቸው ። አስተያየቶቹ በአንቀጽ ፳፫ እንደተጠቀሰው በመንግሥት ብቻ ሳይሆን በኅብረተሰቡ ሌሎች ክፍሎች ተሳትፎ ጭምር የሚከናወኑ ተግባሮች በመሆናቸው የኅብረተሰቡ ኃላፊነት በግልጽ እንዲጠቀስ የሚያመለክቱ ናቸው ።

ከሕዝቡ የቀረቡት አስተያየቶች በትክክል እንዳመለከቱት በአንቀጹ ለተጠቀሱት ጉዳዮች ተግባራዊ መሆን የኅብረተሰቡ ተሳትፎ ወሳኝ ድርሻ የሚኖረው ይሆናል ። ኮሚሽኑ በዚህ ላይ የቀረቡትን ትክክለኛ አስተያየቶች በመቀበል «መንግሥት» ይል የነበረው «መንግሥትና ኅብረተሰብ» በሚለው እንዲተካና « መንግሥት የባህልና የታሪክ ቅርሶች እንዲጠበቁ ፣ ጐጂ ልማዶች እንዲወገዱ ፣ ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በሶሻሊስት ሥነ ምግባር እንዲታነጽና ወዛደራዊ ባህል ደረጃ በደረጃ እንዲሰፍን ያደርጋል ። » ይል የነበረው አንቀጽ ፳፫ ፣

«መንግሥትና ኅብረተሰብ የባህልና የታሪክ ቅርሶች እንዲጠበቁ ፣ ጐጂ ልማዶች እንዲወገዱ ፣ ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በሶሻሊስት ሥነ ምግባር እንዲታነጽና ወዛደራዊ ባህል ደረጃ በደረጃ እንዲሰፍን ያደርጋሉ ። »

ተብሎ እንዲነበብ አሻሽሎታል ።

አገርን መከላከል ፣ ሕብዝንና አብዮትን መጠበቅ በሚለው ምዕራፍ ላይ በሕዝብ የቀረቡ አስተያየቶችና ለረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መዳበር ምክንያት የሆኑ ጉዳዮች በአንቀጽ ፳፭ እና በአንቀጽ ፳፮ ንዑስ አንቀጽ (፩) ላይ የተመሠረቱ ናቸው ። አስተያየቶቹ ሲጠቃለሉ በሁለቱ መካከል ልዩነት ስለሌለ እንዲዋሐዱ ቢደረግ የሚል መልዕክት ያላቸው ናቸው ።

በመሠረቱ « ጽኑ የመከላከያ ኃይል ይኖረዋል » የሚለው ሐረግ ሪፑብሊኩ በዚህ መሠረት በማንኛውም ወቅት አገርን ለመከላከል ፣ ሕዝብንና አብዮትን ለመጠበቅ የሚያስችለው ፣ በባሕርይውም የመደበኛነት ጠባይ ያለው ጠንካራ የመከላከያ ተቋም የሚኖረው መሆኑን የሚያመለክት ነው ። « የአገሪቱን የመከላከል ችሎታ ያጠናክራል» የሚለው ሐረግ ደግሞ ይህ ጽኑ የመከላከያ ኃይል በአንቀጽ ፳፮ ንዑስ አንቀጽ (፪—፬) በተጠቀሱትና በሌሎችም ተመሳሳይ ሁኔታዎች በየጊዜው በእድገት እየተለወጠ የሚሄድ መሆኑን የሚያመለክት ነው ።

የአንቀጾቹ መሠረታዊ መልዕክቶች እነዚህ ሲሆኑ ከሕዝብ የተገኙት አስተያየቶች በምዕራፉ ውስጥ አንድ ለውጥ እንዲደረግ መነሻ ምክንያት ሆነዋል ። ሪፑብሊክ ጽኑ የመካለከያ ኃይል እንደሚኖረው የሚደነግገው እና የዚሁ ኃይል ዓላማ ምን እንደሆነ የሚያመለክተው አንቀጽ ቢጠቃለሉ ከላይ የተመለተውን ይበልጥ ግልጽ እንደሚያደርገውና ቅርጹንም እንደሚያሻሽለው በመታመኑ ኮሚሽኑ አንቀጽ ፳፭ እና አንቀጽ ፳፮ን በአንድ አንቀጽ አጠቃሏቸዋል ። በዚሁ መሠረት አንቀጽ ፳፭ እና አንቀጽ ፳፮ የነበሩት አንቀጽ ፳፭ ሆነው ፣

በረቂቁ አንቀጽ ፲፫ ላይ የሰፈረውም ይህንን መሠረተ ሐሳብ ያጤነ ቢሆንም ሕዝቡ ውይይት ባካሄደበት ወቅት ይህ መሠረተ ሐሳብ የበለጠ ግልጽ ሆኖ እንዲወጣ ያለ ፍላጐትን የሚያመለክቱ አስተያየቶች በመቅረባቸውና ኮሚሽኑም ይህ ሁኔታ በግልጽ ሊንጸባረቅ እንዲችል ሆኖ መቀረጽ እንዳለበት በማመኑ ፡

«የመንግሥት ባለቤትነት የሕዝብ ነው ።»

የሚልና መልዕክቱን በግልጽ ለማስተላለፍ የሚያስችል ንዑስ አንቀጽ የአንቀጽ ፲፫ ንዑስ (፩) ሆኖ እንዲገባ ተደርጓል ።

አብዮቱ ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ እድገት መሠረት የሆኑ አያሌ ሥር ነቀል እርምጃዎችን ወስዷል ። የፖለቲካ ሥልጣን የሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሚሆንበትን ሁኔታ ደረጃ በደረጃ በማደራጀት ከሪፐብሊኩ ምሥረታ ዋዜማ ላይ ደርሷል ። በዚህም የፖለቲካ ሥልጣን ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ በሚበጁ መንገዶች በመጠቀም ማኅበራዊ ባለቤትነትን ለማስፋፋትና በአንጻሩም የግል ባለቤትነትን በስርዓት ለመምራት የሚችልበትን ሁኔታ ሲፈጥር ቆይቷል ።

እነዚህ የባለቤትነት ዓይነቶች ዛሬም በኢትዮጵያ ጐልተው ይታያሉ ። ለሶሻሊስት ሥርዓት ግንባታ መሠረት በመጣል ሂደት ውስጥም የየበኩላቸው ድርሻ ይኖራቸዋል ። በመሆኑም በኢሕዲሪም ማኅበራዊና የግል ባለቤትነት እንደመኖሩና ሚናቸውም በረቂቁ ላይ በግልጽ ሰፍሯል ። በዚህ መሠረት የግል ባለቤትነትም ሕገ መንግሥታዊ ዋስትና አግኝቷል ።

በተለይም የግል ባለቤትነትን መንግሥት ሊወርስ ወይም ሊገዛ ወይም ሊገለገልበት የሚችል መሆኑን በሚያመለክተው አንቀጽ ውስጥ ይህ ዋስትና ጐልቶ እንዲንጸባረቅ ሆኗል ። ይህም « የኅብረተሰቡ ጥቅም» መከበር በግል ባለቤትነት ላይ መንግሥት ለሚወስደው ርምጃ በቀዳሚ ምክንያትነት መኖር ያለበት መሆኑን ከማመልከት ባሻገር መንግሥት ተገቢውን ክፍያ ማድረግ ያለበት መሆኑንም በመደንገግ ነው ።

በውይይቱ ወቅት በሕዝብ የተነሱት ጥያቄዎች መንግሥት በግል ባለቤትነት ሲገለገል ምንም ክፍያ ላያደርግ ነውን ? በሚለው ላይ የመተሠረቱ ናቸው ። የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መልእክት ግን ይህ ስላልነበረ የአንቀጽ ፲፯ ይዘት ይበልጥ ግልጽ እንዲሆን ተደርጓል ። ስለዚህ መንግሥት በግል ባለቤትነት ሊገለገል የሚችለው «ተገቢውን ክፍያ በማድረግ» መሆኑን በግልጽ ለማመልከት እንዲችል « መንግሥት ለኅበረተሰቡ ጥቅም አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘው በሕግ በሚወሰነው መሠረት ማንኛውንም ንብረት ሊገዛ ፡ ሊገለገልበት ወይም ካሣ በመክፈል ሊወርስ ይችላል ። » ይል የነበረው አንቀጽ ፡

«መንግሥት ለኅብረተሰቡ ጥቅም አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘው በሕግ በሚወሰነው መሠረት ማንኛውንም ንብረት ሊገዛ ፡ ተገቢውን ክፍያ በማድረግ ሊገለገልበት ወይም ካሣ በመክፈል ሊወርስ ይችላል ። »

እንዲል ሆኖ ተሻሽሏል ።

የኢኮኖሚ ሥርዓትን በሚመለከተው ምዕራፍ ውስጥ የመልዕክት ጥራትን ለማስገኘት የሚያግዙ ሌሎች ማስተካከያዎችም ተደርገዋል ። በተለይ በአንቀጽ ፲ ንዑስ አንቀጽ (፩) « የዱር አራዊት » ይል የነበረው « የዱር እንስሳት» በሚል መተካቱ ፡ «የግለሰብ ንብረትና ንብረቱን የማስተላለፍ መብት በሕግ መሠረት የተጠበቀ ነው » ይል የነበረው አንቀጽ ፲፮

« የግለሰብ ንብረት በሕግ የተጠበቀ ነው ። የግለሰብ ንብረትን በሕግ መሠረት የማስተላለፍ መብት የተጠበቀ ነው ። »

እንዲል ሆኖ መሻሻሉ ጐላ ያሉና ሊጠቀሱ የሚችሉ ናቸው ።

ማኅበራዊና የባህል ፖሊሲ በሚለው ምዕራፍ ውስጥ ጐላ ያሉ ለውጦች የተደረጉት በአንቀጽ ፲፱ እና በአንቀጽ ፳፫ ላይ ነው ።

የፓርቲውን የመሪነት ሚና ሪፑብሊኩ የሚቀበለው መሆኑ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ውስጥ በግልጽ መደንገጉ ከሚያመለክታቸው በርካታ ጉዳዮች መካከል አንዱ የኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲና መንግሥት መሠረታዊ የሆነውን የአብዮታችንን ዓላማ ከግብ የማድረስ የጋራ አቋም ያላቸው መሆኑን ነው ። ይህን የጋራ አቋም ተግባራዊ በማድረግ ሂደት ፓርቲውና መንግሥት የሚኖራቸው ግንኙነት በልዩ ልዩ መንገድ የሚገለጽ ሲሆን መሠረታዊው ጉዳይ ግን የመንግሥትና የኅብረተሰቡ ተግባራት በፓርቲው ፖሊሲዎች ላይ የተመሠረቱ መሆናቸውን የማረጋገጥ ነው ።

የመከላከያ ኃይላችንን ተቋሞች በተመለከተ የቀረበው ጥያቄ በመሠረቱ በሕገ መንግሥት ደረጃ እንዲገለጹ በማድረግ መልስ የሚያገኝ ሳይሆን አገርን መከላከል ፣ ሕዝብንና አብዮትን መጠበቅ የሚለው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ምዕራፍ በደነገጋቸው መሠረታዊ ጉዳዮች ላይ በመመሥረት በሚወጡ ዝርዝር ሕጎች የሚሸፈን ነው ።

"ገለልተኝነትና ወዛደራዊ ዓለም አቀፋዊነት አይጋጩምን ? የሚለውን ዐይነት ግንዛቤን ለማዳበር ከመፈለግ በርካታ ጥያቄዎች ቀርበዋል ። ገለልተኝነት በዓለም ሠርቶ አደሮች ትግል ከመሳተፍ የሚገታ ፅንስ ሐሳብ አይደለም ። በዚህም ምክንያት ከወዘደራዊ ዓለም አቀፋዊነት ጋር ተደጋጋፊነት ያለው እንጂ የሚቃረን ሆኖ መተርጎም አይኖርበትም ። ሁለቱ ጽንሰ ሐሳቦች የሪፑብሊኩ የውጭ ፖሊሲ ከሚመሠረትባቸው ዋና ዋና መርሖች ከፊሎቹ ናቸው ። በእነዚህና በሰላም አብሮ መኖር መርሖች ላይ በመመሥረት የሚደረጉ ግንኙነቶች ሪፑብሊኩ በዓለም አቀፍ ደረጃ የሚኖረውን ሚና ትክክለኛ መሠረት እንዲኖረው የሚያደርጉ ይሆናሉ ። ጽንሰ ሐሳቦቹ በየራሳቸው የሚቆሙ ቢሆኑም ከአብዮታችን ዓላማዎች ጋር በተያያዘ የምናራምደው የውጭ ፖሊሲ የተሟላ መሠረት እንዲኖረው ለማድረግ እነዚህን መርሖች በሌሎች ዝርዝር ሕጎች ሊሸፈኑ ለሚችሉ ግንኙነቶች ምንጭ እንዲሆኑ በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መመልከታቸው ተደጋጋፊነታቸውን ያመለክታል ።

እንደነዚህ ዐይነት ጥያቄዎች ውይይቱ በተካሄደበት ወቅት በተለያዩ ስልቶች ማብራሪያ የተሰጠባቸው ሲሆን በተከታታይም በሚወሰዱ ከአፈጻጸም ጋር በተያያዙ የማብራራት ርምጃዎችና በሚወጡ ዝርዝር ሕጎች ይዘታቸው ይበልጥ ግልጽ የሚደረግ ይሆናል ።

የተሰነዘሩት የሕዝብ አስተያየቶች ከተመረመሩና ከተተነተኑ በኋላ በረቂቁ ላይ ጉላ ያለ ለውጥ እንዲደረግ መነሻ የሆኑ አስተያየቶች ፦

የመንግሥት ባለቤትነትን የሚደነግገው አንቀጽ የሕዝብ ባለቤትነት በተለያየ መልክ ከሚደነግጉ ካሁን ቀደም በአብዮታዊ መንግሥት የወጡ አዋጆች (ምሣሌ ፦ የገጠርን መሬት የሕዝብ ለማድረግ የወጣ አዋጅ) ከሚሉት የሚጋጭ ስለሚመስል ይስተካከል ፤

—በግል ባለቤትነት ሥር በሚገኙ ንብረቶች መንግሥት ስለሚጠቀምበት ሁኔታ የሚደነግገው አንቀጽ ግለሰቦች ገንዘባቸውን ለአገር እድገት በሚጠቅም መንገድ እንዲያውሉ የሚያበረታታ ሆኖ ይጠናከር ፤

—ስፖርት መዘውተር የሚኖርበት መሆኑ በግልጽ ይመልከት ፤

—የባህልና የታሪክ ቅርሶች መጠበቅን --- ወዘተ የሚደነግገው አንቀጽ ውስጥ የኅብረተሰቡም ኃላፊነት ይገለጽ ፤

—«ጽኑ የመከላከያ ኃይል ይኖረዋል » በሚለውና «የአገሪቱን የመከላከል ችሎታ ያጠናክራል» በሚለው መካከል ምን ልዩነት ስላለ ነው በተለያዩ አንቀጾች እንዲቀረጹ የተደረገው ? የሚሉና የመሳሰሉት ናቸው ።

ረቂቅ ሕገ መንግሥቱ በተለያዩ አንቀጾች በግልጽ እንደሚያመለክተው ሥልጣን የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ነው ። በረቂቁ ላይ የተመለከተውና ከፍተኛው የመንግሥት የሥልጣን አካል የሆነው ብሔራዊ ሸንጎ የዚሁ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነት መግለጫ ነው ። ሌሎች በሕገ መንግሥቱ የተጠቀሱ የመንግሥት አካላት ሁሉ በሕግ የሚሰጣቸውን ሥልጣን በተግባር የሚተረጉሙት የሠርቶ አደሩ ሕዝብ የውክልና የሥልጣን አካል የሆነውን የብሔራዊ ሸንጎን ሥልጣን ተግባራዊ ከማድረግ አንጻር ነው ። ይህ በጥቅሉ የሚያመለክተው በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ውስጥ በሠርቶ አደሩ ሕዝብና በመንግሥት አካላት መካከል የቀረበ መተሳሰር ያለ መሆኑንና የመንግሥት አካላትም የሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን መሣሪያዎች መሆናቸውን ነው ።

«በአርበኞቹ የአምስቱ ዓመታት ትግልና መስዋዕትነትም በፋሺዝም ወረራ ላይ ድልን በመቀዳጀት በታሪክ ተረጋግጦ የቆየውን የነፃነት አርማዋን ከማውለብለብ የሚገታት ኃይልአለመኖሩን እንደገና አስመስክራለች ።»

የሚል ዐረፍተ ነገር በመቅድሙ አራተኛ ፖራግራፍ እንዲገባ ተደርጓል ።

በመቅድሙ ላይ የሕዝብ አስተያየት ያመለከተው ሌላው ጉዳይ በአብዮታችን ታሪክ ውስጥ ለኢትዮጵያ አብዮት አመራር በመስጠት ረገድ ጉልህ ድርሻ ያበረከተው የጊዜያዊ ወታደራዊ አስተዳደር ደርግ ሚና በግልጽ ይጠቀስ የሚል ነው ። ደርግ አብዮታችን ገና ከጅምሩ የነበረበትን የተደራጀ ኃይል አመራር እጦት ከማስወገድም ሌላ ሕዝባዊ አደራን ምንጊዜም ባለመዘንጋት የቀድሞውን ሥርዓት የብዝበዛ መሠረቶች በማስወገድና የሠርቶ አደሩን ሕዝብ ልዕልና ለማረጋገጥ መነሻ የሆኑ ሥር ነቀል ርምጃዎችን በመውሰድ የሠርቶ አደሩን አብዮታዊ ውክልና ይዞ እስከ ሪፑብሊኩ ምሥረታ ስለማድረሱና ታሪካዊ ተልዕኮውን በሚገባ ስለመወጣቱ የቀረበው አስተያየት ትክክለኛነት በኮሚሽኑ ታምኖበታል ። በመሆኑም «አብዮቱ አነሳሱ ላይ የተደራጀ ግንባር ቀደም አመራር ስላልነበረው የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ወገን የሆነው የመለዮ ለባሹ ክፍል ትግሉን አስተባብሮ መምራት ጀመረ ።» ይል የነበረው የመቅድሙ ስምንተኛ ፓራግራፍ፣—

«አብዮቱ በተቀጣጠለበት ወቅት የተደራጀ ግምባር ቀደም አመራር ሰጭ አካል ስላልነበረ ፣ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ወገንና የመለዮ ለባሹ ክፍል አካል የሆነው ጊዜያዊ ወታደራዊ አስተዳደር ደርግ ትግሉን አስተባብሮ መምራት ጀመረ ።»

በሚል እንዲሻሻል ሆኗል ።

ከሕዝብ በቀረበው አስተያየት ላይ በመመሥረት በመቅድሙ የተደረገው ሌላው ጉላ ያለ ማስተካከያ መቅድሙን ከመጀመሪያው እስከ መጨረሻው «እኛ» በሚል የሠርቶ አደሩን ሕዝብ የታሪክ ፣ የክንውኖች እና የሥልጣን ባለቤትነትን በሚያመለክት መልክ ማስተካከል ነው ። በመሠረተ ሃሳብ ደረጃ ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በመቅድሙ ላይ ለተጠቀሱት ጉዳዮች ባለቤት መሆኑ በመጀመሪያው ረቂቅ ላይም ተመልክቶ ነበር ። ሆኖም የቀረበው አስተያየት አጻጻፉ ለሕዝብ ውይይት በቀረበው ረቂቅ ላይ እንደተመለከተው በመጨረሻ ላይ ብቻ ሳይሆን አንድ ወጥ በሆነ መንገድ ይስተካከል የሚል ስለነበር ለዚህ አስተያየት ተገቢውን ግምት በመስጠት ኮሚሽኑ አስፈላጊ በሆነበት ቦታ ሁሉ ማስተካከያ አድርጓል ።

## 3.2 ክፍል አንድ—ሥርዓተ ማኅበርን በሚመለከት

የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ክፍል አንድ የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የሚያራምዳቸውን የፖለቲካና የኢኮኖሚ ሥርዓቶች ፣ ማኅበራዊና ባህላዊ ፖሊሲዎች እንደዚሁም አገርን ስለመከላከል ፣ ሕዝብንና አብዮቱን ስለመጠበቅና የውጭ ፖሊስን የሚመለከቱ ጉዳዮችን ያካተተ ነው ።

የፖለቲካ ሥርዓቱን በሚገልጹት አንቀጾች የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነት፣ የኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲ የመሪነት ሚናና ሕዝቡ በሕዝባዊ ድርጅቶቹ መድረክነት በአገሪቱ ፖለቲካዊ ፣ ኢኮኖሚያዊና ማኅበራዊ ሕይወት ውስጥ ሙሉ ተሳታፊ እንደሚሆን በማያሻማ ተደንግጓል ። ሠርቶ አደሩ የሥልጣን ባለቤትነቱን ተግባራዊ የሚያደርግ

ከሕዝብ የቀረቡት ጥያቄዎች ፣ አስተያየቶችና ሐሳቦች ተተንትነው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱን ይዘት ለማሻሻል የሚረዱት ተወስደው ጥቅም ላይ ወለዋል ።

በዚሁ መሠረት በመቅድሙ ላይ ሁለት አዳዲስ ፍሬ ሐሳቦች ፣ በቀረው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ክፍሎች ደግሞ አምስት አዳዲስ ንዑሳን አንቀጾች ገብተዋል ። በመቅድሙና በ12 የረቂቁ አንቀጾች ላይ ደግሞ ይዘትን የሚለውጡ ማስተካከያዎች ተደርገዋል ። ሁለት ራሳቸውን ችለው ተቀርጸው የነበሩት አንቀጾች በአንድ አንቀጽ እንዲጠቃለሉ በመደረጉ ለሕዝብ ውይይት ቀርቦ በነበረው ረቂቅ ላይ 120 የነበሩት አንቀጾች ለውሳኔ ሕዝብ በቀረበው ላይ 119 ሆነዋል ። በመቅድሙ አሥራ አንድ ፓራግራፎችና በተከታታይ በሚገኙ 40 አንቀጾች ላይ አዳዲስ ሐረጐችንና ቃላትን በመጨመር ፣ የነበሩትን በማስወጣት ፣ ሌሎች ማሻሻያዎችን በማድረግ የመልዕክት ጥራትን የሚያስገኙ 138 ማስተካከያዎች ተደርገዋል ። ከነዚህም ሌላ የሰነዱን ጥራት ለመጠበቅ በርካታ ሆሄያትና ነጥቦች ተስተካክለዋል ።

## 3. በረቂቅ ሕገ መንግሥቱ ልዩ ልዩ ክፍሎች ላይ በሕዝቡ ውይይት የተነሱ ዋና ዋና ሃሳቦችና የተደረጉ ለውጦች

### 3.1. መቅድሙን በሚመለከት

የረቂቅ ሕገ መንግሥቱን መቅድም ይዘት ለማሻሻል ምክንያት የሆኑ ዋና ዋና የሕዝብ አስተያየቶች ፦

—የዓድዋ ድል ብቻ ለምን ተጠቀሰ ?

—በፋሺዝም ላይ የተገኘው ድል ቢገለጽ ፤

—በመቅድሙ ላይ የሰፈረው በሙሉ ሥርዓ አደሩ ሕዝብ በባለቤትነት የሚገልጸው መሆኑን በሚያመለክት መልኩ ቢጠናከር ፤

—የጊዜያዊ ወታደራዊ አስተዳደር ደርግ ሚና በተገቢው ሁኔታ ቢገለጽ

የሚሉ ናቸው ።

እንደሚታወቀው የረቂቅ ሕገ መንግሥቱ መቅድም ከጥንት ጀምሮ የኢትዮጵያ ሕዝብ ነፃነቱን በማስከበር ያካበተውን አኩሪ ታሪክ ፣ ዛሬ የሚገኝበትን የእድገት ደረጃና የወደፊቱን የጉዞ አቅጣጫ ባጭሩ የሚያመለክት ነው ። ያለፈውን የኢትዮጵያን ሕዝብ አኩሪ የነፃነት ታሪክ የሚያመለክቱ አያሌ ክንውኖች በተለያዩ ወቅቶች በጉንደት ፣ በጉራዕ ፣ በዶጋሊ እና በመሳሰሉት የትግል ጉራዎች የተፈጸሙ መሆናቸው በኢትዮጵያውያንና በዓለም ኅብረተሰብም ይታወቃል ። እነዚህ ክንውኖች ሁሉ በየበኩላቸው ለአንድነታችንና ለነፃነታችን መረጋገጥ ከፍተኛ ድርሻ ማበርከታቸው ዕውቅ ሲሆን በተለይ በኢምፔሪያሊስቶችና በቅኝ ገዥዎች ላይ የተቀዳጀነው የዓድዋ ድል ለሌላው የዓለም ኅብረተሰብ ጭምር ምሳሌ በመሆን አኩሪ ታሪካችንን ያደሰ ታላቅ ክንውን መሆኑ የሚካድ አይደለም ።

ስለዚህም የአድዋ ድል በወቅቱ ለነበሩት የአገሪቱ ዜጐችና ለተከታታይ ትውልዶች ክብርን ያቀዳጀ ፣ ለመላው የዓለም ፀረ ኢምፔሪያሊስት ትግልና በተለይም ለአፍሪካ ሕዝቦች የነፃነትን ፋና ያሳየ ድል በምሳሌነት እንዲጠቀስ ተደርጎ ነበር ። ይህ ድል ብቻውን መጠቀሱ በዚህ የአርአያነት ጠባዩ ሌሎችንም ወካይ ሆኖ እንዲታይ እንጂ ታሪክ ክቡር ቦታ የሰጣቸውን ሌሎች ድሎቻችንን በመዘንጋት አይደለም ።

ሆኖም ከሕዝብ የተገኘው አስተያየት የኢትዮጵያ ሕዝብ በፋሺዝም ላይ የተቀዳጀው ድል ከዓድዋው ድል ጋር ተያይዞ ሊተረጎም የሚገባውና ታሪካችንንም ያደሰ ተግባር ሆኖ በመገኘቱ ሊጠቀስ ይገባል የሚልነው ። ሐሣቡም በኮሚሽኑ ተቀባይነትን በማግኘቱ ፣

፲. የአገሪቱን ጥቅም ፣ የሕዝቡን ደኅንነትና የዜጐችን መብት ለማስከበርና ለማረጋገጥ አስፈላጊውን ሕጋዊ እርምጃ ይወስዳል ፤

፲፩. ሕግና ሥርዓት መከበሩን ያረጋግጣል ፤

፲፪. ከብሔራዊ ሸንጐ ፣ ከመንግሥት ምክር ቤትና ከሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት የሚሰጡትን ሌሎች ተግባሮች ያከናውናል ፤

፲፫. ስለ ሥራው እንቅስቃሴ ለብሔራዊ ሸንጐና ሸንጐው በማይሰበሰብበት ጊዜ ለመንግሥት ምክር ቤትና ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት በየወቅቱ ዘገባ ያቀርባል ።

## አንቀጽ ፺፫

ጠቅላይ ሚኒስትር የሚከተሉት ሥልጣንና ተግባር ይኖሩታል ፦

፩. የሚኒስትሮች ምክር ቤትን ይሰበስባል ፤ ሥራውን ይመራል ፤ ያስተባብራል ፤

፪. የሚኒስትሮች ምክር ቤትን ይወክላል ፤

፫. በሚኒስትሮች ምክር ቤት የወጡ ደንቦችና የተሰጡ ውሳኔዎች በሥራ ላይ መዋላቸውን ያረጋግጣል ፤

፬. ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮችንና ሌሎች የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባላትን በዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፹፮ ንዑስ አንቀጽ ፩ (ለ) መሠረት ለማስመረጥ ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ያቀርባል ፤

፭. በመንግሥት ምክር ቤትና በሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት የሚሰጡትን ሌሎች ተግባሮች ያከናውናል ።

## አንቀጽ ፺፬

የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባላት በወል ለሚወስዱት እርምጃ የጋራ ፣ በተናጠል ለሚወስዱት እርምጃ የግል ኃላፊነት አለባቸው ።

# ምዕራፍ ዐሥራ ሦስት

# የአስተዳደር አካባቢና የራስ ገዝ አካባቢ የሥልጣንና የአስተዳደር አካላት

## አንቀጽ ፺፭

የአስተዳደር አካባቢና የራስ ገዝ አካባቢ ከፍተኛ የመንግሥት ሥልጣን አካል የአካባቢው ሸንጐ ነው ።

## አንቀጽ ፺፮

፩. የአካባቢ ሸንጐዎች የሥራ ዘመን በሕግ ይወሰናል ።

፪. የሸንጐዎቹ የስብሰባ ጊዜ በሕግ ይወሰናል ።

## አንቀጽ ፺፯

የአስተዳደር አካባቢና የራስ ገዝ አካባቢ ሸንጐ የሚከተሉት ሥልጣንና ተግባር ይኖሩታል ፦

፩. የመንግሥት ሕጐች ፣ ውሳኔዎችና መመሪያዎች በሥራ ላይ መዋላቸውን ያረጋግጣል ፤

፪. ለበታች ሸንጐዎች መመሪያ ይሰጣል ፤ ሥራቸውን ያስተባብራል ፤ ይቆጣጠራል ፤

፫. የአካባቢውን ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ ዕቅዶችና በጀት ይወስናል ፣ በብሔራዊ ሸንጐ ሲጸድቁም በሥራ ላይ ያውላል ፤

፬. በሥልጣኑ ክልል ውስጥ የሚገኙ የሥራ እንቅስቃሴዎችን የሚመለከቱ መመሪያዎች ይሰጣል ፤

፭. የአካባቢውን ፍርድ ቤት ዳኞች ይመርጣል ፤

፮. የአካባቢውን ሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴ ሊቀመንበር ይመርጣል ፤

፯. ከአባላቱ መካከል የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴ ይመርጣል ፤ ሥራውንም ይቆጣጠራል ፤

«በዚህ ሸንጎና በኢትዮጵያ ሕዝብ ፊት ይህን ታሪካዊ ኃላፊነት ስቀበል ፤ የኢትዮጵያን ሉዓላዊነት ፣ ነፃነትና አንድነት በቆራጥነት ለመጠበቅ ፤ ለሶሻሊዝም ግንባታ ፣ ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ ደኅንነት ፤ ፍላጐትና ጥቅም መከበር ፤ ለብሔረሰቦች እኩልነት መረጋገጥ በሐቀኝነትና ባለመታከት ለመሥራት ፤ ለዚህ ሕገ መንግሥትና ለሌሎች የአገሪቱ ሕጎች ተገዥ ለመሆን ፤ ምን ጊዜም ለኢትዮጵያ ክብር ፣ እድገትና ብልጽግና በታማኝነት ለማገልገል ቃል እገባለሁ ። »

## ምዕራፍ ዐሥራ ሁለት

## የሚኒስትሮች ምክር ቤት

### አንቀጽ ፹፱

፩ የሚኒስትሮች ምክር ቤት ማለትም መስተዳድሩ የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ከፍተኛ አስፈጻሚና አስተዳደራዊ አካል ነው ።

፪ የሚኒስትሮች ምክር ቤት ጠቅላይ ሚኒስትር ፣ ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮች ፣ ሚኒስትሮችና በሕግ በሚወሰነው መሠረት ሌሎች አባላት የሚገኙበት ምክር ቤት ነው ።

### አንቀጽ ፺

፩. በዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፷፫ ንዑስ አንቀጽ ፬ (መ) እና አንቀጽ ፹፯ ንዑስ አንቀጽ ፩ (ለ) መሠረት የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባላት በብሔራዊ ሸንጎ ይመረጣሉ ።

፪. የሚኒስትሮች ምክር ቤት የሥራ ዘመን የብሔራዊ ሸንጎ የሥራ ዘመን ይሆናል ። አዲስ የሚኒስትሮች ምክር ቤት እስኪመረጥ ድረስ ያለው የሚኒስትሮች ምክር ቤት በሥራ ላይ ይቆያል ።

፫. የሚኒስትሮች ምክር ቤት ተጠሪነቱ ለብሔራዊ ሸንጎ ነው ። ሸንጎው በማይሰበሰብበት ጊዜ ተጠሪነቱ ለመንግሥት ምክር ቤትና ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ይሆናል ።

### አንቀጽ ፺፩

የሚኒስትሮች ምክር ቤት ጠቅላይ ሚኒስትሩ ፣ ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮችና በሕግ በሚወሰነው መሠረት ሌሎች አባላት የሚገኙበት ቋሚ ኮሚቴ ይኖረዋል ።

### አንቀጽ ፺፪

የሚኒስትሮች ምክር ቤት የሚከተሉት ሥልጣንና ተግባር ይኖሩታል ፦

፩. በብሔራዊ ሸንጎ ፣ በመንግሥት ምክር ቤትና በሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት የወጡ ሕጎችና የተሰጡ ውሳኔዎች በሥራ መተርጐማቸውን ያረጋግጣል ፤ ደንቦችን ያወጣል ፤ መመሪያዎችን ይሰጣል ፤

፪. የሚኒስቴሮችን ፣ የብሔራዊ ኮሚቴዎችን ፣ የኮሚሽኖችንና በቀጥታ ለሚኒስትሮች ምክር ቤት ተጠሪ የሆኑትን ሌሎች የመንግሥት አስተዳደር አካላት ሥራ ይመራል ፣ ያስተባብራል ፤

፫. የአስተዳደር አካባቢና የራስ ገዝ አካባቢ ሸንጎዎች የሥራ አስፈጻሚ ኮሚቴዎችን ሥራ ይቆጣጠራል ፤

፬. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፪ እና ፫ የተመለከቱት አካላት ውሳኔዎች ሕግን የሚፃረሩ ሆነው
ሲገኙ ይሽራል ፤ እንዳስፈላጊነቱም እንዲስተካከሉ መመሪያ ይሰጣል ፤

፭. የማኅበራዊና የኢኮኖሚ ዕቅዶችን ያዘጋጃል ፤ ለብሔራዊ ሸንጎ ያቀርባል ፤ ሲጸድቁም ተግባራዊነታቸውን ያረጋግጣል ፤

፮. ዓመታዊ በጀትን ያዘጋጃል ፤ ለብሔራዊ ሸንጎ ያቀርባል ፤ ሲጸድቅም ተግባራዊነቱን ያረጋግጣል ፤

፯. የገንዘብና የፋይናንስ ፖሊሲን ተግባራዊነት ያረጋግጣል ፤

፰. ስለ ሪፑብሊኩ የውጭ ግንኙነት ለብሔራዊ ሸንጎ ፣ ለመንግሥት ምክር ቤትና ለሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ሐሳብ ያቀርባል ፣ ሲወሰንም ተግባራዊነቱን ያረጋግጣል ፤

፱. መንግሥታዊ የግልግል ሥራ ያደራጃል ፣ ይመራል ፤

፪. ሪፑብሊኩን በውስጥና በውጭ ይወክላል ፤
፫. የጦር ኃይሎች ጠቅላይ አዛዥ ነው ።

## አንቀጽ ፹፮

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት የሚከተሉትን ሥልጣንና ተግባር በዚህ ሕገ መንግሥትና በሌሎች ሕጐች መሠረት ያከናውናል ፦

፩. ሀ. የአገሪቱ የውስጥና የውጭ ፖሊሲ በተግባር መተርጐሙን ያረጋግጣል ፤
ለ. ጠቅላይ ሚኒስትርን ፣ በጠቅላይ ሚኒስትሩም አቅራቢነት ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮችንና ሌሎች የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባላትን ለብሔራዊ ሸንጐ አቅርቦ ያስመርጣል ፤
ሐ. የሚኒስትሮች ምክር ቤት የተሰጠውን ኃላፊነት መወጣቱን ያረጋግጣል ፣ እንዳስፈላጊነቱም ምክር ቤቱን ይሰበስባል ፤
መ. የጠቅላይ ፍርድ ቤት ፕሬዚዳንትን ፣ ምክትል ፕሬዚዳንቶችንና ዳኞችን ፣ ጠቅላይ ዐቃቤ ሕግን ፣ የብሔራዊ ሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴ ሊቀ መንበርንና ዋና ኦዲተርን ለብሔራዊ ሸንጐ አቅርቦ ያስመርጣል ፤
ሠ. ጠቅላይ ፍርድ ቤት ፣ የጠቅላይ ዐቃቤ ሕግ መሥሪያ ቤት ፣ ብሔራዊ የሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴና የዋና ኦዲተር መሥሪያ ቤት የተሰጣቸውን ኃላፊነት መወጣታቸውን ያረጋግጣል ።

፪. ሀ. ዓለም አቀፍ ውሎችን ይዋዋላል ፤
ለ. ዲፕሎማቲክ ግንኙነቶችን ይመሠርታል ፤ ዲፕሎማቲክ መልእክተኞችን ይሾማል ፤
ሐ. የውጭ አገር ዲፕሎማቲክ መልእክተኞችን የሹመትና የስንብት ደብዳቤ ይቀበላል ።

፫. ሀ. የመከላከያ ምክር ቤት አባላትን ይሾማል ፤ ምክር ቤቱንም ይሰበስባል ፤
ለ. ከፍተኛ የመንግሥት የሲቪልና የውትድርና ማዕረጐችን ይሰጣል ፤
ሐ. ከፍተኛ የመንግሥት ባለሥልጣኖችን ሹመት ያስታውቃል ፤
መ. ይቅርታ ያደርጋል ።

፬. የሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት በዚህ አንቀጽ የተሰጡትን ሥልጣንና ተግባር በሥራ ላይ ለማዋል ሕግ ሲያስፈልግ የፕሬዚዳንት ድንጋጌዎችን ያወጣል ።

፭. ሀ. በብሔራዊ ሸንጐ ፣ በመንግሥት ምክር ቤትና በሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት የሚወጡትን ሕጐች በነጋሪት ጋዜጣ ያውጃል ፤
ለ. በብሔራዊ ሸንጐ የሚሰጡትን ሌሎች ተግባሮች ያከናውናል ፤
ሐ. ስለሥራው እንቅስቃሴ ለብሔራዊ ሸንጐ ዘገባ ያቀርባል ።

## አንቀጽ ፹፯

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት ብሔራዊ ሸንጐ በማይሰበሰብበት ጊዜ አስገዳጅ ሁኔታ ሲፈጠር ፦
ሀ. ጠቅላይ ሚኒስትርን ፣ በእርሱም አቅራቢነት ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮችንና ሌሎች የምክር ቤቱ አባላትን ይሾማል ፣ ይሽራል ፤
ለ. የጠቅላይ ፍርድ ቤት ፕሬዚዳንትን ፣ ምክትል ፕሬዚዳንቶችንና ዳኞችን ፣ ጠቅላይ ዐቃቤ ሕግን ፣ የብሔራዊ ሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴ ሊቀ መንበርንና ዋና ኦዲተርን ይሾማል ፣ ይሽራል ።

፪. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፩ መሠረት የሚደረጉ ውሳኔዎች በፕሬዚዳንት ልዩ ድንጋጌ የሚታወጁ ሆነው ለሚቀጥለው የብሔራዊ ሸንጐ ስብሰባ ቀርበው መጽደቅ ይኖርባቸዋል ።

## አንቀጽ ፹፰

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት ሥራውን ከመጀመሩ በፊት በብሔራዊ ሸንጐ የሚከተለውን ቃል ይገባል ፦

## አንቀጽ ፹፪

የመንግሥት ምክር ቤት የሚከተሉት ሥልጣንና ተግባር ይኖሩታል ፡—

፩. ሀ. የሕገ መንግሥትንና የሌሎች ሕጎችን ተግባራዊነት ያረጋግጣል ፤
ለ. ሕገ መንግሥትንና ሌሎች ሕጎችን ይተረጉማል ፤
ሐ. በብሔራዊ ሸንጎ ፡ በመንግሥት ምክር ቤትና በሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ከወጡት ሕጎች ጋር የሚቃረኑ ተጠሪነታቸው ለሸንጎው የሆኑ የመንግሥት አካላት የሚያወጡዋቸውን ደንቦችና መመሪያዎች ይሽራል ፤
መ. ዓለም አቀፍ ውሎችን ያጸድቃል ፡ ይሠርዛል ፤
ሠ. ምሕረት ያደርጋል ፤
ረ. ዜግነትን ይሰጣል ፤
ሰ. የፖለቲካ ጥገኝነትን ይሰጣል ፤
ሸ. ሜዳይ ፡ ኒሻንና ሽልማት ይሰጣል ።
፪. ሀ. የብሔራዊ ሸንጎንና የአካባቢ ሸንጎዎችን የምርጫ ቀን ያስታውቃል ፤
ለ. የብሔራዊ ሸንጎ መደበኛና አስቸኳይ ጉባኤዎችን ይጠራል ፤
ሐ. የብሔራዊ ሸንጎ ቋሚና ጊዜያዊ ኮሚሽኖችን ሥራ ያስተባብራል ፤
መ. የመከላከያ ምክር ቤትን ያቋቁማል ፤
ሠ. የሚኒስትሮች ምክር ቤት ፡ ጠቅላይ ፍርድ ቤት ፡ ጠቅላይ ዐቃቤ ሕግ ፡ ብሔራዊ የሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴና ዋና ኦዲተር የተሰጣቸውን ኀላፊነት መወጣታቸውን ይከታተላል ፤
ረ. በብሔራዊ ሸንጎ የሚሰጡትን ሌሎች ተግባሮች ያከናውናል ፤
ሰ. ስለሥራው እንቅስቃሴ ለብሔራዊ ሸንጎ ዘገባ ያቀርባል ።
፫. የመንግሥት ምክር ቤት በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፩ እና ፪ የተሰጡትን ሥልጣንና ተግባር በሥራ ላይ ለማዋል ሕግ ሲያስፈልግ ድንጋጌዎችን ያወጣል ።

## አንቀጽ ፹፫

፩. የመንግሥት ምክር ቤት ብሔራዊ ሸንጎ በማይሰበሰብበት ጊዜ አስፈላጊ ሆኖ ሲገኝ የዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፩፻፲፱ እንደተጠበቀ ሆኖ ልዩ ድንጋጌዎችን ያወጣል ።
፪. የመንግሥት ምክር ቤት ብሔራዊ ሸንጎ በማይሰበሰብበት ጊዜ አስገዳጅ ሁኔታ ሲፈጠር ፡ የአስቸኳይ ጊዜ ሁኔታን ፤ ጦርነትን ፡ የጦር ጊዜ አስተዳደርን ፤ ክተትን ወይም ሰላምን ሊያውጅ ይችላል ።
፫. በዚህ አንቀጽ ንዑስ አንቀጽ ፩ እና ፪ መሠረት የሚወጡ ልዩ ድንጋጌዎች ለሚቀጥለው የብሔራዊ ሸንጎ ስብሰባ ቀርበው መጽደቅ ይኖርባቸዋል ።

# ምዕራፍ ዐሥራ አንድ

# የሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት

## አንቀጽ ፹፬

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት በዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፷፫ ንዑስ አንቀጽ ፬ (ሀ) መሠረት በብሔራዊ ሸንጎ ይመረጣል ፡ ተጠሪነቱም ለብሔራዊ ሸንጎ ነው ። የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት የሥራ ዘመን የብሔራዊ ሸንጎ የሥራ ዘመን ይሆናል ።

## አንቀጽ ፹፭

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት ፡—

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ርዕሰ መንግሥት ነው ፤

## አንቀጽ ፷፭

፩. አንድ የሕዝብ እንደራሴ ከባድ ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተገኘ በስተቀር ያለ ብሔራዊ ሸንጎ ወይም ሸንጎው ባልተሰበሰበበት ጊዜ ያለ መንግሥት ምክር ቤት ፈቃድ አይያዝም ፤ በወን ጀልም አይከሰስም ።

፪. አንድ የሕዝብ እንደራሴ በሸንጐውና በሸንጐው አካላት ስብሰባዎች ላይ በሚሰጠው አስተያየት ምክንያት አይጠየቅም ፤ አይከሰስም ።

## አንቀጽ ፷፮

፩. የሕዝብ እንደራሴዎች በመንግሥት አካላት የወጡ ሕጐችንና የተላለፉ ውሳኔዎችን አፈጻጸም ይከ ታተላሉ ።

፪. የሕዝብ እንደራሴዎች ለመንግሥት አካላት ፣ ለሕዝባዊና ለሌሎች ድርጅቶች ጥያቄ የማቅረብ መብት አላቸው ፤ ተጠያቂዎቹም ተገቢውን መልስ የመስጠት ግዴታ አለባቸው ።

## አንቀጽ ፷፯

የሕዝብ እንደራሴዎች መደበኛ ሥራቸውን እንደያዙ ይቆያሉ ። የእንደራሴነት ተግባራቸውን ለማ ከናወን እንዲችሉ ሊሟሉ የሚገባቸው ሁኔታዎች በሕግ ይወሰናሉ ።

## አንቀጽ ፷፰

፩. እያንዳንዱ የሕዝብ እንደራሴ ለመረጠው ሕዝብ በብሔራዊ ሸንጐው የወጡ ሕጐችንና የተላለፉ ውሳኔዎችን የማብራራትና ከመረጠው ሕዝብ አስተያየትን የመቀበል ፣ ለሚቀርብለት ጥያቄም ተገቢ መልስ የመስጠት ኃላፊነት አለበት ።

፪. እያንዳንዱ የሕዝብ እንደራሴ ለመረጠው ሕዝብ ስለሥራው እንቅስቃሴ በየወቅቱ ዘገባ ያቀርባል ።

## አንቀጽ ፷፱

አንድ የሕዝብ እንደራሴ ሥራውን ከመጀመሩ በፊት የሚከተለውን ቃል ይገባል ፡

«ለኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ነፃነትና አንድነት ለመቆም ፣ ለሶሻ ሊዝም ታማኝ ለመሆን ፣ የሠርቶ አደሩን ሕዝብ ፍላጐትና ጥቅም ለማስቀደም ፣ ለዚህ ሕገ መንግሥትና ለሌሎችም ሕጐች ተፈጻሚነት ለመሥራት ቃል እገባለሁ ።»

## አንቀጽ ፸

የብሔራዊ ሸንጐን የአሠራር ሥርዓት እንደዚሁም የሕዝብ እንደራሴዎችን ጥቆማ ፣ ምርጫ ፣ ተጠ ሪነት ፣ ልዩ መብት ፡ ተግባርና የውክልና መሠረዝ የሚመለከቱት የዚህ ሕገ መንግሥት አንቀ ጾች በማንኛውም ደረጃ ለሚቋቋሙ ሸንጐዎችና ለሚመረጡ የሕዝብ እንደራሴዎች እንደአግባቡ ተፈጻሚነት ይኖራቸዋል ።

# ምዕራፍ ዐሥር

# የመንግሥት ምክር ቤት

## አንቀጽ ፸፩

፩. የመንግሥት ምክር ቤት በዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፷፫ ንዑስ አንቀጽ ፫ (ሀ) መሠረት የሚቋቋም ፣ የብሔራዊ ሸንጐ ቋሚ አካል ሆኖ የሚሠራ የመንግሥት ሥልጣን አካል ነው ።

፪. የመንግሥት ምክር ቤት ፕሬዚዳንት ፣ ምክትል ፕሬዚዳንቶች ፣ ጸሐፊና አባላት ይኖሩታል ።

፫. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ፕሬዚዳንት የመንግሥት ምክር ቤት ፕሬዚዳንት ነው ።

፬. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ምክትል ፕሬዚዳንት የመንግሥት ምክር ቤት ምክ ትል ፕሬዚዳንት ነው ።

፪. የብሔራዊ ሸንጐ አባላት ምርጫ የሕዝብን ብዛት መሠረት ያደርጋል ።

፫. በምርጫው ሂደት ብሔረሰቦች በብሔራዊ ሸንጐ መወከላቸው ይረጋገጣል ።

## አንቀጽ ፶፮

የመረጠው ሕዝብ እምነት ያጣበትን የብሔራዊ ሸንጐ አባል ውክልና የመሠረዝ መብት አለው ።

## አንቀጽ ፶፯

ብሔራዊ ሸንጐ በዓመት አንድ ጊዜ መደበኛ ስብሰባ ያደርጋል ። አስቸኳይ ስብሰባ በመንግሥት ምክር ቤት ወይም በሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ውሳኔ ወይም ከአባላቱ ከሦስት አንዱ እጅ ሲጠይቅ ይጠራል።

## አንቀጽ ፶፰

፩. የብሔራዊ ሸንጐ የሥራ ዘመን አምስት ዓመት ይሆናል ።

፪. የሸንጐው የሥራ ዘመን ከመፈጸሙ ሁለት ወር በፊት የአዲሱ ሸንጐ ጠቅላላ ምርጫ ይከናወናል። የነባሩ ሸንጐ የሥራ ዘመን እንደተፈጸመ ያለው የመንግሥት ምክር ቤት አዲሱን ሸንጐ ይጠራል።

፫. አዲሱ ሸንጐ እንደተሰበሰበ የመጀመሪያ ተግባሩ በዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፶፫ ንዑስ አንቀጽ ፬ የተመለከቱትን የመንግሥት አካላት አባላት መምረጥ ይሆናል ።

፬. አዲስ የተመረጠው ሸንጐ ተሰብስቦ የመንግሥት ምክር ቤትንና የሪፑብሊኩን ፕሬዚዳንት እስከ ሚመርጥበት ጊዜ ድረስ ያለው የመንግሥት ምክር ቤትና ያለው ፕሬዚዳንት በሥልጣን ላይ ይቆያሉ።

## አንቀጽ ፶፱

በጦርነት ጊዜ ወይም ሌላ አስቸኳይ ሁኔታ ሲያጋጥም ብሔራዊ ሸንጐ ሁኔታው እስከ ሚወገድበት ጊዜ ድረስ የሥራ ዘመኑን ሊያራዝም ይችላል ።

## አንቀጽ ፷

ብሔራዊ ሸንጐ ለሥራው አስፈላጊ የሆኑ ቋሚና ጊዜያዊ ኮሚሽኖችን ያቋቁማል ።

## አንቀጽ ፷፩

የመንግሥት ምክር ቤት ፥ የሪፑብሊኩ ፕሬዚዳንት ፥ የብሔራዊ ሸንጐ ኮሚሽኖች ፥ የብሔራዊ ሸንጐ አባላት ፥ የሚኒስትሮች ምክር ቤት ፥ ጠቅላይ ፍርድ ቤት ፥ ጠቅላይ ዐቃቤ ሕግ ፥ ከፍተኛ የአስተ ዳደር አካባቢና የራስ ገዝ አካባቢ ሸንጐዎች እና በአገር አቀፍ አካሎቻቸው አማካይነት ሕዝባዊ ድርጅቶች ሕግን የማመንጨት መብት አላቸው ።

## አንቀጽ ፷፪

፩. ብሔራዊ ሸንጐ ከአባላቱ ከሦስት ሁለት እጅ ሲገኙ ምልዓተ ጉባኤ ይኖረዋል ።

፪. ማንኛውም አዋጅና የሸንጐው ውሳኔ ከተገኙት አባላት ከግማሽ በላይ በሆነ የድምፅ ብልጫ ሲደገፍ እንደጸደቀ ይቆጠራል ። ሆኖም በዚህ ሕገ መንግሥት አንቀጽ ፩፻፲፱ የተደነገገው እንደተጠበቀ ነው።

## አንቀጽ ፷፫

ብሔራዊ ሸንጐ የሚያደርጋቸው ስብሰባዎች በዝግ እንዲሆኑ ካልወሰነ በስተቀር በግልጽ ይካሄዳሉ።

## አንቀጽ ፷፬

የብሔራዊ ሸንጐ አባላት የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ባለሙሉ ሥልጣን እንደራሴዎች ናቸው ።

## አንቀጽ ፷፫

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ብሔራዊ ሸንጐ በማንኛውም የአገር ጉዳይ ላይ ውሳኔ የመስጠት ሥልጣን አለው ። ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ ብሔራዊ ሸንጐ የሚከተሉት ሥልጣንና ተግባር ይኖሩታል ፦

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክን
   ሀ. ሕገ መንግሥትና አዋጆች ያወጣል ፤ ያሻሽላል ፤ አፈጻጸማቸውንም ይቆጣጠራል ፤
   ለ. የውስጥና የውጭ ፖሊሲ ይወስናል ፤
   ሐ. የመከላከያና የደኅንነት ፖሊሲ ይወስናል ፤
   መ. የሰላምና የጦርነት ሁኔታ ይወስናል ፤
   ሠ. የአጭርና የረጅም ጊዜ የማኅበራዊና የኢኮኖሚ ዕቅዶች ያጸድቃል ፤
   ረ. ዓመታዊ በጀት ያጸድቃል ፤
   ሰ. የገንዘብና የፋይናንስ ፖሊሲ ይወስናል ።
፪. የአስተዳደር አካባቢዎችንና ራስ ገዝ አካባቢዎችን
   ሀ. ይመሠርታል ፤ ክልላቸውን ፤ ደረጃቸውንና ተጠሪነታቸውን ይወስናል ፤
   ለ. የሚተዳደሩበትን አዋጅ ያወጣል ፤
   ሐ. የገቢ ምንጫቸውን ይወስናል ።
፫. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክን
   ሀ. የመንግሥት ምክር ቤት ፤
   ለ. የሚኒስትሮች ምክር ቤት ፤ ሚኒስቴሮች ፤ ብሔራዊ ኮሚቴዎች ፤ ኮሚሽኖችና ባለሥልጣኖች ፤
   ሐ. ጠቅላይ ፍርድ ቤት ፤
   መ. የጠቅላይ ዐቃቤ ሕግ መሥሪያ ቤት ፤
   ሠ. ብሔራዊ የሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴ እና
   ረ. የዋና ኦዲተር መሥሪያ ቤት ፤
   ያቋቁማል ።
፬. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክን
   ሀ. ፕሬዚዳንት ፤
   ለ. ምክትል ፕሬዚዳንት ፤
   ሐ. የመንግሥት ምክር ቤት ምክትል ፕሬዚዳንቶች ፤ ጸሐፊና አባላት ፤
   መ. በአንቀጽ ፹፮ ንዑስ አንቀጽ ፩ (ለ) መሠረት ሲቀርብለት ጠቅላይ ሚኒስትር ፤ ምክትል ጠቅላይ ሚኒስትሮችና ሌሎች የሚኒስትሮች ምክር ቤት አባላት ፤
   ሠ. በአንቀጽ ፹፮ ንዑስ አንቀጽ ፩ (መ) መሠረት ሲቀርብለት የጠቅላይ ፍርድ ቤት ፕሬዚዳንት ፤ ምክትል ፕሬዚዳንቶችና ዳኞች ፤ ጠቅላይ ዐቃቤ ሕግ ፤ የብሔራዊ ሠርቶ አደር ቁጥጥር ኮሚቴ ሊቀ መንበር እና ዋና ኦዲተር
   ይመርጣል ።
፭. አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘው በከፍተኛ የአገር ጉዳዮች ላይ ውሳኔ ሕዝብ እንዲሰጥባቸው ያደርጋል ።
፮. የአባላቱን የምርጫ ውጤት ትክክለኛነት ያረጋግጣል ።

## አንቀጽ ፷፬

ለብሔራዊ ሸንጐ አባልነት ዕጩዎች በኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲ አካላት ፤ በሕዝባዊ ድርጅቶች ፤ በወታደር ክፍሎችና በሌሎች በሕግ መብት በተሰጣቸው አካላት ይጠቆማሉ ።

## አንቀጽ ፷፭

፩. የብሔራዊ ሸንጐ አባላት ምርጫ ሁሉ አቀፍ ፤ እኩል ፤ ርቱዕና በምሥጢር ይሆናል ።

### አንቀጽ ፶፭

፩. ኢትዮጵያውያን ሶሻሊስት ንብረትን የመጠበቅና የመንከባከብ ግዴታ አለባቸው ።

፪. መንግሥትና ኅብረተሰብ የታሪክ መዘክሮችንና የባህል ቅርሶችን ለመጠበቅ ፣ ለመንከባከብ ፣ ለማሰባሰብና ከጥቅም ላይ ለማዋል በሚያደርጉት ጥረት ኢትዮጵያውያን የመካፈል ግዴታ አለባቸው።

፫. ኢትዮጵያውያን ተፈጥሮንና የተፈጥሮ ሀብትን በተለይም ደንን የማልማትና የአፈርና የውሀ ሀብትን የመጠበቅና የመንከባከብ ግዴታ አለባቸው ።

### አንቀጽ ፶፮

ኢትዮጵያውያን የጾታና የሥራ ዓይነት እኩልነት እንዲከበር ፤ በብሔረሰቦች ሠርቶ አደሮች መካከል መቀራረብ ፣ መከባበርና ለሶሻሊስት ሥርዓት ግንባታ በጋራ የመሥራት ባህል እንዲሰፍን የማገዝ ግዴታ አለባቸው ።

### አንቀጽ ፶፯

ማንኛውም ኢትዮጵያዊ የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሕገ መንግሥትንና ሕጎችን ማክበርና የኢትዮጵያዊነትን ክብርና ሞገስ መጠበቅ ግዴታው ነው ።

### አንቀጽ ፶፰

የዜጎች ነፃነቶችና መብቶች አጠቃቀምና የግዴታዎች አከባበር በሕግ ይወሰናል ። የዜጎች ነፃነቶችና መብቶች አጠቃቀም በሕግ ገደብ የሚደረግበት የመንግሥትና የኅብረተሰብ ጥቅም ፣ እንደዚሁም የሌሎች ግለሰቦች ነፃነቶችና መብቶች እንዲከበሩ ብቻ ነው ።

# ክፍል ሦስት

# የመንግሥት አወቃቀርና አሠራር

## ምዕራፍ ስምንት

## ቅርጸ መንግሥት

### አንቀጽ ፶፱

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ በአስተዳደር አካባቢዎችና በራስ ገዝ አካባቢዎች የሚዋቀር አሐዳዊ መንግሥት ነው ።

### አንቀጽ ፷

፩. የአስተዳደር አካባቢዎች በተዋረድ ከከፍተኛ እስከ መሠረታዊ የሚገኙ የአስተዳደር አሐዶች ናቸው።

፪. የአስተዳደር አካባቢዎች ክልል ፣ ደረጃና ተጠሪነት በሕግ ይወሰናል ።

### አንቀጽ ፷፩

፩. የራስ ገዝ አካባቢዎች እንዳስፈላጊነቱ ልዩ ልዩ የአስተዳደር አሐዶች ይኖሯቸዋል ።

፪. የራስ ገዝ አካባቢዎች ክልል ፣ ደረጃና ተጠሪነት በሕግ ይወሰናል ።

## ም ዕ ራ ፍ ዘ ጠ ኝ

## ብሔራዊ ሸንጎ

### አንቀጽ ፷፪

በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ከፍተኛው የመንግሥት ሥልጣን አካል ብሔራዊ ሸንጎ ነው ።

## አንቀጽ ፵፯

፩· የኢትዮጵያውያን የንግግር ፡ የጽሑፍ ፡ የመሰብሰብ ፡ ሰላማዊ ትዕይንተ ሕዝብ የማድረግና በማኅበር የመደራጀት ነፃነት የተረጋገጠ ነው ።

፪· መንግሥት ለነዚህ ነፃነቶች ተግባራዊ መሆን አስፈላጊውን ቁሳዊና ሞራላዊ ድጋፍ ይሰጣል ።

## አንቀጽ ፵፰

፩· የኢትዮጵያውያን ከቦታ ወደ ቦታ የመዘዋወር ነፃነት የተረጋገጠ ነው ።

፪· ማንኛውም ኢትዮጵያዊ በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ግዛት ውስጥ የመኖርያ ስፍራ የመለዋወጥ ነፃነት አለው ።

## አንቀጽ ፵፱

የኢትዮጵያውያን የመልእክት ምሥጢርነት የተረጋገጠ ነው ።

## አንቀጽ ፶

፩· ኢትዮጵያውያን የመምረጥና የመመረጥ መብት አላቸው ።

፪· ማንኛውም ኢትዮጵያዊ የአዕምሮ መታወክ ከሌለበትና የመምረጥና የመመረጥ መብቱ በሕግ የተገፈፈ ካልሆነ በስተቀር የብሔረሰብ ፡ የጾታ ፡ የሃይማኖት ፡ የሥራ ዓይነት ፡ የማኅበራዊና የሌላም ሁኔታ ልዩነት ሳይደረግበት ፲፰ ዓመት ሲሞላው ለመንግሥት ሥልጣን አካላት አባላትን የመምረጥና ፳፩ ዓመት ሲሞላው ለአባልነት የመመረጥ መብት አለው ። ዝርዝሩ በሕግ ይወሰናል ።

## አንቀጽ ፶፩

፩· ኢትዮጵያውያን የመንግሥትና የሕዝባዊ ድርጅቶችን አሠራር በሚመለከት አስተያየትና በማስረጃ የተደገፈ ሒስ የማቅረብ መብት አላቸው ።

፪· ጉዳዩ የሚመለከታቸው ባለሥልጣኖችና ተቋሞች የቀረበውን አስተያየትና ሒስ መርምረው መልስ መስጠትና ተገቢውን እርምጃ መውሰድ ይኖርባቸዋል ። አስተያየትና ሒስ ባቀረበ ዜጋ ላይ የጥቃት እርምጃ መውሰድ በሕግ ያስቀጣል ።

## አንቀጽ ፶፪

ኢትዮጵያውያን በመንግሥት አካላትና በሕዝባዊ ድርጅቶች ወይም በባለሥልጣኖቻቸው ላይ አቤቱታ የማቅረብ መብት አላቸው ። የቀረበው አቤቱታ መመርመርና መልስ ማግኘት አለበት ።

## አንቀጽ ፶፫

፩· የእናት አገርን ደኅንነት ፡ አብዮቱንና የሠርቶ አደሩን ሕዝብ ድሎች መጠበቅ የእያንዳንዱ ኢትዮጵያዊ ታላቅ ክብር ፡ ከፍተኛ ተግባርና ግዴታ ነው ።

፪· እናት አገርን መክዳት ከፍተኛ ቅጣት የሚያስከትል በሕዝብ ላይ የሚፈጸም እጅግ ከባድ ወንጀል ነው ።

፫· ብሔራዊ ውትድርና አገልግሎት የማንኛውም ኢትዮጵያዊ መብትና ግዴታ ነው ። አፈጻጸሙ በሕግ ይወሰናል ።

## አንቀጽ ፶፬

ኢትዮጵያውያን ሥራ ማኅበራዊ ጠቀሜታ ያለው የሰው ልጅ ሕይወት መሠረት መሆኑን በመረዳት ፡ የሚሠራም በውጤቱ ተጠቃሚ መሆኑን በመገንዘብ ፡ በየተሰማሩበት የሥራ መስክ ኃላፊነታቸውንና የሥራ ዲሲፕሊንን አክብረው ፡ የንብረት እንክብካቤ በማድረግና ምርታማነታቸውን በማሳደግ የመሥራት ግዴታ አለባቸው ።

## አንቀጽ ፵

፩. ኢትዮጵያውያን ነፃ ትምህርት የማግኘት መብት አላቸው ።
፪. መንግሥት ዕድሜያቸው ለትምህርት ለደረሱ ሕፃናት የግዴታ ትምህርት ደረጃ በደረጃ እንዲዳረስ ያደርጋል ፤ በዓይነታቸውና በደረጃቸው የተለያዩ ትምህርት ቤቶችንና የሙያ ማሠልጠኛ ተቋሞችን ያስፋፋል ።

## አንቀጽ ፵፩

፩. ኢትዮጵያውያን በሳይንስ ፣ በቴክኖሎጂና በሥነ ጥበባት ምርምሮችንና የፈጠራ ሥራዎችን የማካሄድ ነፃነት አላቸው ።
፪. መንግሥት ዜጎች የሚያደርጉትን የምርምርና የፈጠራ ሥራዎች ያበረታታል ፤ ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ ኑሮ እድገትና ለሶሻሊዝም ግንባታ መፋጠን ለሚረዱ የምርምርና የፈጠራ ተግባራት ልዩ ድጋፍ ይሰጣል ።

## አንቀጽ ፵፪

፩. ኢትዮጵያውያን የጤና እንክብካቤ የማግኘት መብት አላቸው ።
፪. መንግሥት የጤና ተቋሞችን ደረጃ በደረጃ በማስፋፋት የጤና አገልግሎትን ይሰጣል ።

## አንቀጽ ፵፫

፩. የኢትዮጵያውያን ሰብዕና አለመደፈር የተረጋገጠ ነው ።
፪. የኢትዮጵያውያን መኖሪያ ቤት አለመደፈር የተረጋገጠ ነው ። ሕግ ከሚደነግገው በስተቀር ማንም ሰው ያለ ባለቤቱ ፈቃድ ከሌላው ሰው መኖሪያ ቤት መግባት አይችልም ።

## አንቀጽ ፵፬

፩. ማንኛውም ሰው ወንጀል ሲፈጽም እጅ ከፍንጅ ካልተገኘ ወይም በዐቃቤ ሕግ ትዕዛዝ ወይም በፍርድ ቤት ውሳኔ ካልሆነ ወይም ሕግ ከሚደነግገው በስተቀር አይያዝም ።
፪. ማንኛውም የተያዘ ሰው በ፵፰ ሰዓት ውስጥ ወደ ፍርድ ቤት መቅረብ አለበት ፤ ሆኖም ይህ ጊዜ ወደ አቅራቢያው ፍርድ ቤት ለመድረስ የሚያስፈልገውን ጊዜ አይጨምርም ።

## አንቀጽ ፵፭

፩. ማንኛውም ሕግን በመጣስ በወንጀል የተከሰሰ ሰው በፍርድ ቤት ካልተወሰነበት በስተቀር ጥፋተኛ ሆኖ አይቆጠርም ።
ተከሳሹን የሚረዳ ካልሆነ በስተቀር የወንጀል ሕግ ወደኋላ ተመልሶ አይሠራም ።
ማንኛውም ተከሳሽ ራሱ የመከላከል ወይም የሕግ ጠበቃ የማቆም መብት አለው ። በከባድ ወንጀል ተከስሶ የሕግ ጠበቃ ለማቆም አለመቻሉ ለተረጋገጠለት ሰው በሕግ በሚወሰነው መሠረት መንግሥት በነፃ ያቆምለታል ።
ማንኛውም ሰው በራሱ ላይ ካልሆነ ወይም ሕግ ከሚደነግገው በስተቀር ሕጋዊ ምስክርነት የመስጠት ግዴታ አለበት ፤ ሆኖም በኃይል ወይም በተፅዕኖ እንዲመሰክር አይገደድም ። በኃይል ወይም በተፅዕኖ የተገኘ ምስክርነት ሕጋዊነት አይኖረውም ።

## አንቀጽ ፵፮

የኢትዮጵያውያን የኅሊናና የሃይማኖት ነፃነት የተረጋገጠ ነው ።
የሃይማኖት ነፃነት አጠቃቀም የአገርንና የአብዮትን ደኅንነት እንደዚሁም የሕዝብን መልካም ሥነ ምግባርና የሌላውን ዜጋ ነፃነት የሚነካ መሆን የለበትም ።
መንግሥትና ሃይማኖት የተለያዩ ናቸው ። የሃይማኖት ድርጅቶች ሕጋዊ አቋም በሕግ ይወሰናል ።

፪. መንግሥት አንድን ኢትዮጵያዊ ለሌላ መንግሥት አሳልፎ አይሰጥም ።

### አንቀጽ ፴፫

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ለብሔራዊ አርነት ፡ ለፀረ ዘረኝነት ፡ ለሰላምና ለዲሞክራሲ በሚያደርጉት ትግል ምክንያት ጥቃት ለሚያደርስባቸው የውጭ አገር ሰዎች ጥገኝነትን ይሰጣል ።

### አንቀጽ ፴፬

፩. በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ግዛት ውስጥ የሚገኙ የውጭ አገር ዜጎችና ዜግነት የሌላቸው ግለሰቦች በሕግ የተረጋገጡ ነፃነቶች ፡ መብቶችና ግዴታዎች አሏቸው ።
፪. መንግሥት የውጭ አገር ዜጋንና ዜግነት የሌለው ግለሰብን በዓለም አቀፍ ስምምነት መሠረት ካልሆነ በስተቀር ለሌላ መንግሥት አሳልፎ አይሰጥም ።

## ምዕራፍ ሰባት

## የዜጎች መሠረታዊ ነፃነቶች ፡ መብቶችና ግዴታዎች

### አንቀጽ ፴፭

፩. ኢትዮጵያውያን በብሔረሰብ ፡ በጾታ ፡ በሃይማኖት ፡ በሥራ ዓይነት ፡ በማኅበራዊና በሌላም ሁኔታ ልዩነት ሳይደረግባቸው በሕግ ፊት እኩል ናቸው ።
፪. የኢትዮጵያውያን እኩልነት በፖለቲካ ፡ በኢኮኖሚ ፡ በማኅበራዊና በባህል መስኮች ሁሉ በእኩልነት በመሳተፍ ይረጋገጣል ።

### አንቀጽ ፴፮

፩. በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሴቶችና ወንዶች እኩል መብት አላቸው ።
፪. ሴቶች በፖለቲካ ፡ በኢኮኖሚ ፡ በማኅበራዊና በባህል መስኮች ከወንዶች ጋር በእኩልነት እንዲሳተፉ መንግሥት በተለይ በትምህርት ፡ በሥልጠናና በሥራ ልዩ ድጋፍ ይሰጣል ።
፫. መንግሥት ለሴቶች በእርግዝናና በወሊድ ጊዜ የጤና እንክብካቤ እንዲደረግላቸው ፡ ምቹ የሥራ ሁኔታ እንዲኖራቸውና በቂ የዕረፍት ጊዜ እንዲያገኙ ተገቢ እርምጃዎች ደረጃ በደረጃ እንዲወሰዱ ያደርጋል ።

### አንቀጽ ፴፯

፩. ጋብቻ ለአካለ መጠን በደረሱ በአንድ ሴትና በአንድ ወንድ መካከል በፈቃደኝነት ላይ የተመሠረተ ነው ። ባልና ሚስት በቤተሰብ ግንኙነታቸው እኩል መብት አላቸው ። ጋብቻ የመንግሥት ጥበቃ ይደረግለታል ።
፪. ልጆች በጋብቻም ሆነ ከጋብቻ ውጭ ቢወለዱ እኩል መብት አላቸው ።

### አንቀጽ ፴፰

፩. ኢትዮጵያውያን የመሥራት መብት አላቸው ።
፪. መንግሥት ብሔራዊ የኢኮኖሚ እድገትን መሠረት በማድረግ ደረጃ በደረጃ የሥራ ዕድሎች እንዲፈጠሩ ፡ የሥራ ሁኔታዎች እንዲሻሻሉ ያደርጋል ።

### አንቀጽ ፴፱

፩. የሠርቶ አደሩ የዕረፍት መብት የተጠበቀ ነው ።
፪. መንግሥት የሥራ ሰዓቶችንና የዕረፍት ጊዜያትን ይወስናል ፡ ደረጃ በደረጃም ለሠርቶ አደሩ ዕረፍት የሚጠቅሙ ማኅበራዊ አገልግሎቶች እንዲስፋፉ ያደርጋል ።

# ምዕራፍ አምስት

# የውጭ ጉዳይ ፖሊሲ

## አንቀጽ ፳፯

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የውጭ ፖሊሲ በወዛደራዊ ዓለም አቀፋዊነት ፣ በሰላም አብሮ መኖርና በገለልተኝነት መርሖች ላይ የተመሠረተ ነው ።

## አንቀጽ ፳፰

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የአገሪቱን ጥቅም በማስከበር ከሁሉም አገሮች ጋር በእኩልነትና በጋራ ጥቅም ላይ የተመሠረተ ግንኙነትንና ትብብርን ያዳብራል ። አገሮች በሚመርጡት ማኅበራዊና ኢኮኖሚያዊ ሥርዓት የመኖር መብታቸውን ያከብራል ።

፪. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ከሶሻሊስት አገሮች ጋር ሁለገብ ግንኙነትንና ትብብርን ያዳብራል ፤ ከዓለም አቀፍ የሠራተኛ መደብ ንቅናቄ ፣ ከአብዮታዊ ዲሞክራሲያዊ ኃይሎች ፣ ከብሔራዊ አርነት ንቅናቄዎችና ከሌሎች ዲሞክራሲያዊና ሰላም ወዳድ ኃይሎች ጋር ግንኙነቱን ያጠናክራል ።

፫. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ኢምፔሪያሊዝምን ፣ቀጥተኛና የእጅ አዙር ቅኝ አገዛዝን ፣ ዘረኝነትንና ሌሎችንም የጭቆናና የብዝበዛ ገጽታዎች በጽኑ ይታገላል ።

## አንቀጽ ፳፱

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የማይገሰሰው የአገሮች ብሔራዊ ሉዓላዊ[illegible] የግዛት አንድነትን ፣ አንዱ በሌላው የውስጥ ጉዳይ ጣልቃ አለመግባባትን ፣ አለመግባባቶችን [illegible]ም መፍታትን ፣ ባጠቃላይም የገለልተኝነት መርሖችን መሠረት በማድረግ ለሕዝቦች መደጋገፍ ፣ ለጋራ ልማትና ከጐረቤት አገሮች ጋር በመልካም ጉርብትና ላይ ለተመሠረተ ግንኙነት መጠናከር ጥረት ያደርጋል ።

## አንቀጽ ፴

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ለሰው ልጅ ሰላም ፣ ደኅንነትና እድገት በቆሙ ዓለም አቀፍና አህጉራዊ ድርጅቶች ውስጥ ንቁ ተሳትፎ ያደርጋል ።

# ክፍል ሁለት

# ዜግነት ፣ ነፃነቶች ፣ መብቶችና ግዴታዎች

# ምዕራፍ ስድስት

# ዜግነት

## አንቀጽ ፴፩

፩. ማንኛውም ሰው ወላጆቹ ወይም ከወላጆቹ አንዱ ኢትዮጵያዊ ከሆኑ ኢትዮጵያዊ ነው ።

፪. ዜግነትን የሚመለከቱ ዝርዝር ጉዳዮች በሕግ ይወሰናሉ ።

፫. የውጭ አገር ዜጎችና ዜግነት የሌላቸው ግለሰቦች የኢትዮጵያን ዜግነት የሚያገኙበት ሁኔታና ሥርዓት በሕግ ይወሰናል ።

## አንቀጽ ፴፪

፩. መንግሥት ከኢትዮጵያ ግዛት ውጭ የሚገኙትን ኢትዮጵያውያን መብትና ጥቅም ያስከብራል ።

፪. መንግሥትና ኅብረተሰብ ሕፃናት በሳይንሳዊ አስተሳሰብ ታንጸው፣ በሥነ ምግባር ፣ በአእምሮና በአካል ጠንክረው፡ የአገር ፍቅር ያላቸውና ለሶሻሊዝም የቆሙ ዜጎች ሆነው እንዲያድጉ ልዩ እንክብካቤ ያደርጋሉ ።

## አንቀጽ ፷፩

መንግሥትና ኅብረተሰብ የሕዝቡን ደኅንነት ለማሻሻል የጤና፣ የጡረታ፣ የመድንና የሌላም ማኅበራዊ ዋስትና አገልግሎቶችን ደረጃ በደረጃ ያስፋፋሉ ።

## አንቀጽ ፷፪

የኢትዮጵያን ሉዓላዊነትና የግዛት አንድነት ሲያስከብሩና አብዮቱን ሲጠብቁ ጉዳት ለደረሰባቸው ታጋዮችና መሥዋዕት ለሆኑትም ታጋዮች ቤተሰቦች መንግሥትና ኅብረተሰብ ልዩ እንክብካቤ ያደርጋሉ።

## አንቀጽ ፷፫

መንግሥትና ኅብረተሰብ የባህልና የታሪክ ቅርሶች እንዲጠበቁ፣ ጎጂ ልማዶች እንዲወገዱ፣ ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በሶሻሊስት ሥነ ምግባር እንዲታነጽና ወዛደራዊ ባህል ደረጃ በደረጃ እንዲሰፍን ያደርጋሉ።

# ምዕራፍ አራት

# አገርን መከላከል ፣ ሕዝብንና አብዮትን መጠበቅ

## አንቀጽ ፷፬

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሉዓላዊነቱንና የግዛት አንድነቱን ያስከብራል ፣ አብዮቱንም ይጠብቃል ።

፪. የአገርን ሕልውናና አብዮቱን መጠበቅ የመላው ሠርቶ አደር ሕዝብ ታሪካዊ ኃላፊነት ነው ።

## አንቀጽ ፷፭

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ጽኑ የመከላከያ ኃይል ይኖረዋል ።

፪. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የመከላከያ ኃይል ለአገር አንድነትና ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ የበላይነት ፣ ለሰላምና ለሶሻሊዝም የቆመና የሚታገል የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ሠራዊት ነው ።

## አንቀጽ ፷፮

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የአገሪቱን የመከላከል ችሎታ ያጠናክራል ።

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የሠርቶ አደሩን ሕዝብ የአርበኝነትና የአብዮታዊ ጀግንነት መንፈስ ያዳብራል ፤ አገርን ለመከላከል ፣ ሕዝብንና አብዮትን ለመጠበቅ እንዳስፈላጊነቱ መላውን ሠርቶ አደር ሕዝብ ያንቀሳቅሳል ።

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የወጣቱን ሶሻሊስት አርበኝነት ስሜት ያሳድጋል ፤ የብሔራዊ ውትድርና አገልግሎትንም በተግባር ያውላል ።

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የተፈጥሮና ሰው ሠራሽ አደጋዎችን ለመቋቋም ሲቪል መከላከያን ያደራጃል ።

የመንግሥትና የኅብረት ሥራ ማኅበራት ባለቤትነት ፣ የግል ባለቤትነትና በሕግ የሚወሰኑ ሌሎች የባለቤትነት ዓይነቶች ናቸው ።

## አንቀጽ ፲፫

፩. የመንግሥት ባለቤትነት የሕዝብ ነው።
፪. መንግሥት ቁልፍ የሆኑ የማምረቻ ፣ የማከፋፈያና የአገልግሎት ድርጅቶችን በባለቤትነት በመያዝ በኢኮኖሚው መሪ ሚና ይኖረዋል ። የተፈጥሮ ሀብት በተለይም መሬት፡ የማዕድን ሀብት፣ ውሃና ደን የመንግሥት ንብረት ነው ። የተፈጥሮ ሀብት ልማትና አጠቃቀም በሕግ ይወሰናል ።

## አንቀጽ ፲፬

መንግሥት የኅብረት ሥራ ማኅበራት ባለቤትነት ሚና እያደገ እንዲሄድ አስፈላጊውን ድጋፍ ይሰጣል፣ ያበረታታል ።

## አንቀጽ ፲፭

የግል ባለቤትነት በመንግሥት ፖሊሲ እየተመራ ለብሔራዊ ኢኮኖሚ አስተዋጽኦ የሚያደርጉ እንቅስቃሴዎችን እንዲያካሂድ ይደረጋል። የግል ባለቤትነትን በሕግ መሠረት የማስተላለፍ መብት የተጠበቀ ነው።

## አንቀጽ ፲፮

የግለሰብ ንብረት በሕግ የተጠበቀ ነው ። የግለሰብ ንብረትን በሕግ መሠረት የማስተላለፍ መብት የተጠበቀ ነው።

## አንቀጽ ፲፯

መንግሥት ለኅብረተሰቡ ጥቅም አስፈላጊ ሆኖ ሲያገኘው በሕግ በሚወሰነው መሠረት ማንኛውንም ንብረት ሊገዛ፣ ተገቢውን ክፍያ በማድረግ ሊገለገልበት ወይም ካሣ በመክፈል ሊወርስ ይችላል ።

## አንቀጽ ፲፰

፩. ሥራ የተከበረ የኅብረተሰቡ የሀብትና የደኅንነት ምንጭ ነው ። የማንኛውም ሰው ማኅበራዊ አቋም የሚወሰነው በሥራው ነው ።
፪. መንግሥት «ከእያንዳንዱ እንደችሎታው ለእያንዳንዱ እንደሥራው» የሚለውን መርሕ ደረጃ በደረጃ ተግባራዊ ያደርጋል ።
፫. መንግሥት የኅብረተሰቡን ሥራ ወዳድነት፣ የሥራ ችሎታና ፈጠራ እንዲዳብር ያደርጋል ።

# ምዕራፍ ሦስት

# ማኅበራዊና የባህል ፖሊሲ

## አንቀጽ ፲፱

፩. መንግሥት የዜጐችን የአእምሮና የአካል እድገትና የሥራ ብቁነት በማዳበር አዲስ ባህልን ለመገንባትና ለሶሻሊዝም መሠረት ለመጣል ትምህርትና ሌሎች የዕውቀት ማበልጸጊያ አገልግሎቶች እንዲስፋፉ ያደርጋል ።
፪. መንግሥትና ኅብረተሰብ ዜጐች የአካል ማሠልጠን እንቅስቃሴንና ስፖርትን እንዲያዘወትሩ አስፈላጊውን ድጋፍ ይሰጣሉ ።

## አንቀጽ ፳

፩. ቤተሰብ የኅብረተሰቡ መሠረት ስለሆነ መንግሥትና ኅብረተሰብ ልዩ ልዩ ማኅበራዊ አገልግሎቶችንና ሌሎችንም ድጋፎች በመስጠት ይንከባከቡታል ።

## አንቀጽ ፮

፩. በማርክሲዝም ሌኒኒዝም የሚመራው የኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲ ሠርቶ አደሩን ሕዝብ ለማገልገልና ጥቅሙንም ለማስከበር የቆመ ግንባር ቀደም ፓርቲ ነው ።
፪. የኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲ የአገሪቱ የእድገት አቅጣጫ ቀያሽ ፥ የመንግሥትና የመላው ኅብረተሰብ መሪ ኃይል ነው ።
፫. የፓርቲው አካላት ሁሉ የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሕገ መንግሥትን ያከብራሉ ።

## አንቀጽ ፯

ሕዝባዊ ድርጅቶች በአገሪቱ ፖለቲካዊ ፥ ኢኮኖሚያዊ ፥ ማኅበራዊና ባህላዊ ሕይወት ለሕዝብ ተሳትፎ መድረኮች ናቸው ። በመንግሥት ፖሊሲ አወጣጥና አፈጻጸም ይሳተፋሉ ።

## አንቀጽ ፰

የኢትዮጵያ የፖለቲካ ሥርዓት እድገት አቅጣጫ ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በመንግሥትና ወሳኝ በሆኑ የኅብረተሰቡ ጉዳዮች ላይ ያለውን ተሳትፎ በማሳደግ ፥ የመንግሥት አካላትን አደረጃጀትና አሠራር በማሻሻል ፥ የሠርቶ አደሩን ሕዝብ ቁጥጥር በማጠናከር ፥ የሕዝባዊ ድርጅቶችን ሚና በማዳበር ፥ የመንግሥትንና የኅብረተሰቡን ተግባራት ሕጋዊ መሠረት በማጠናከር ለሶሻሊስት ሥርዓት ግንባታ መሠረት የመጣሉን ሂደት ማፋጠን ይሆናል ።

# ምዕራፍ ሁለት
# የኢኮኖሚ ሥርዓት

## አንቀጽ ፱

፩. መንግሥት የኢኮኖሚው ግንባታ መሠረታዊ ዓላማ የሆነውን የሠርቶ አደሩን ሕዝብ የኑሮና የባህል እድገት ያዳብራል ።
፪. መንግሥት ሶሻሊስት የምርት ግንኙነትን ደረጃ በደረጃ በማስፋፋትና በማጠናከር በሳይንስና ቴክኖሎጂ ተጠቅሞ የምርት ኃይሎችን እድገት በማፋጠን አገሪቱን ከኢኮኖሚ ኋላቀርነት ያላቅቃል ።
፫. መንግሥት ውስጣዊ ትደጋጋፊነቱና ተዛምዶው ጠንካራ የሆነ ብሔራዊ ኢኮኖሚን ይገነባል ፤ በገጠርና በከተማ ፥ በጠረፍና በመሀል አገር ያለውን የኢኮኖሚ ግንኙነትም በጥብቅ ያስተሳስራል ።

## አንቀጽ ፲

፩. መንግሥት የተፈጥሮ ሚዛን እንዲጠበቅ ያደርጋል ፤ የተፈጥሮ ሀብት በተለይም መሬት ፥ ውሃ ፥ ደንና የዱር እንስሳት እንክብካቤ እንዲያገኙና እንዲዳብሩ በማድረግ ለሠርቶ አደሩ ሕዝብ ጥቅም መዋላቸውን ያረጋግጣል ።
፪. መንግሥት ለልማት አመቺ ሁኔታን ለመፍጠር የሕዝቡን አሰፋፈር ከተፈጥሮ ሀብት ሥርጭት ጋር እንዲመጣጠን ያደርጋል ።
፫. መንግሥት የገጠርን ኑሮ ከኋላቀርነት ለማላቀቅና ሕዝቡን ለተሻለ ማኅበራዊ ሕይወት ለማብቃት ተበታትኖ የሚኖረው ሕዝብ እንዲሰባሰብ ያበረታታል ።

## አንቀጽ ፲፩

መንግሥት የአገሪቱን የኢኮኖሚና ማኅበራዊ እንቅስቃሴ በማእከላዊ ዕቅድ ይመራል ።

## አንቀጽ ፲፪

በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የምርት መገልገያ ባለቤትነት ሶሻሊስት ማለትም

# ክፍል አንድ
# ሥርዓተ ማኅበር
## ምዕራፍ አንድ
## የፖለቲካ ሥርዓት

### አንቀጽ ፩

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ በሠራተኛውና በገበሬው ኅብረት ፣ በምሁሩ ፣ በአብዮታዊ ሠራዊት ፣ በእደ ጥበብ ባለሙያውና በሌሎች ዲሞክራሲያዊ የኅብረተሰብ ክፍሎች ትሳትፎ ላይ የተ መሠረተ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ መንግሥት ነው ።

፪. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ደሴቶቹን ጨምሮ የየብስ ፣ የአየርና የባህር ግዛቱ የማይ ነጣጠልና የማይደፈር ሉዓላዊ መንግሥት ነው።

፫. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ብሔራዊ ዲሞክራሲያዊ አብዮትን እያጠናቀቀ ለሶሻሊ ሊዝም ግንባታ መሠረት ይጥላል ።

### አንቀጽ ፪

፩. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሁሉም ብሔረሰቦች በእኩልነት የሚኖሩበት አሐዳዊ መንግሥት ነው ።

፪. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የብሔረሰቦችን እኩልነት ያስከብራል ፣ ትምክሕተኝነት ንና ጠባብነትን ይዋጋል ፣ የሁሉንም ብሔረሰቦች ሠርቶ አደሮች አንድነት ያጠናክራል ።

፫. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ በተለይ በዝቅተኛ ደረጃ በሚገኙት ላይ ትኩረት በማ ድረግ የብሔረሰቦችን ያልተመጣጠነ የኢኮኖሚ እድገት ደረጃ በደረጃ በማስተካከል የጋራ ብል ጽግናቸውን ያረጋግጣል ።

፬. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የአካባቢ የራስ በራስ አስተዳደርን ተግባራዊ ያደርጋል ።

፭. የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የብሔረሰቦች ቋንቋዎች እኩልነትን ፣ መዳበርንና መከ በርን ያረጋግጣል ።

### አንቀጽ ፫

፩. በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ ሥልጣን የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ነው ።

፪. ሠርቶ አደሩ ሕዝብ የሥልጣን ባለቤትነቱን ተግባራዊ የሚያደርገው በምርጫ በሚያቋቁማቸው ብሔ ራዊ ሸንጎና የአካባቢ ሸንጎዎች አማካይነት ነው ። የሌሎች የመንግሥት አካላት ሥልጣን ከነዚህ የመንግሥት ሥልጣን አካላት ይመነጫል ።

፫. ሠርቶ አደሩ ሕዝብ ሥልጣኑን በውሳኔ ሕዝብም ተግባራዊ ያደርጋል ።

### አንቀጽ ፬

፩. በኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የመንግሥት አካላት አደረጃጀትና አሠራር በዲሞክራ ሲያዊ ማእከላዊነት መርሕ ላይ የተመሠረተ ነው።

፪. ከዝቅተኛ እስከ ከፍተኛ ደረጃ የሚገኙ የመንግሥት ሥልጣን አካላት በምርጫ ይቋቋማሉ ። የመን ግሥት ሥልጣን አካላት ማእከላዊ አመራርንና የአካባቢ ሐሳብ አመንጭነትን በተግባር ያሁላሉ ። የበላይ አካላት ውሳኔዎች በበታች አካላት ተፈጻሚ ይሆናሉ ። የበታች አካላት ለበላይ አካላት ተጠሪ ናቸው ።

### አንቀጽ ፭

የመንግሥት አካላት ፣ ሕዝባዊ ድርጅቶች ፣ ሌሎች ማኅበራት ፣ ባለሥልጣኖቻቸው ፣ እንደዚሁም ማን ኛውም ግለሰብ ሶሻሊስት ሕጋዊነትን ያከብራሉ ።

ትርፍ ቤቶች፣ ታላላቅ የማምረቻ፣ የማከፋፈያና አገልግሎት ሰጭ ተቋሞች የሕዝብ ሀብት ሆነዋል። ለብሔረሰብ፣ ለጾታና ለሃይማኖት እኩልነት ሁኔታዎች ተመቻችተዋል። ሠርቶ አደሩ ሕዝብ በየፈርጁ እየተደራጀ በአገሩ ጉዳይ ወሳኝ የሚሆንበት መብት ሊቀዳጅ ችሏል።

እኛ የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ ፍትሕ፣ እኩልነትና ብልጽግና የሰፈነበትን የአዲሱን ኅብረተሰብ ግንባታ ትግል በውል ለመያያዝ የበቃነው በቀላሉ አይደለም። የመደብ ጠላቶቻችን ከፊታችን የደቀኗቸውን ብርቱ ፈተናዎች መወጣት ቀዳሚ ተግባራችን ነበር። ቀድሞም ለነፃነታችንና ለአንድነታችን መከበር ስንዋደቅ እንደኖርን ሁሉ ዛሬ ደግሞ «አብዮታዊት እናት አገር ወይም ሞት» ብለን በመነሳት ለዓላማችን ግብ መምታት እየተፋለምን አሁን ለምንገኝበት ለፈጣን ማኅበራዊ እድገት አመቺ ወቅት ልንበቃ ችለናል።

በአሁኑ ጊዜ እኛ የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ ዋና ትኩረታችን በልማት ላይ ሲሆን፣ በአጠቃላይ ዓላማችንም ብሔራዊ ዲሞክራሲያዊ አብዮትን እያጠናቀቅን ለሶሻሊዝም ግንባታ ተፈላጊውን ቁሳዊና ቴክኒካዊ መሠረት መጣል ነው። ይሁን እንጂ ፀረ አብዮትና ፀረ ሶሻሊዝም የሆኑ ኢምፔሪያሊስትና የአድኅሮት ኃይሎች ሐቀኛ የእድገት ጉዟችንን ለማደናቀፍ ከመሞከር ስለማይታቀቡ ይህን አድራጎታቸውን መቋቋም ሌላው የትግላችን ግንባር ነው።

እኛ የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ የመራራ ትግላችን ውጤት የሆነውን የኢትዮጵያ ሠራተኞች ፓርቲን አመራር የተቀዳጀን በመሆኑ፣ የፖለቲካ ባህላችንን እያዳበርን ዓላማችንን ከግብ ለማድረስ በምንችልበት አስተማማኝ ሁኔታ ላይ እንገኛለን። በዚህ መሠረት የአባቶቻችንን አደራ ከማስከበር ጋር የአዲስ ሥርዓተ ማኅበር ግንባታን ታሪካዊ ተግባር በስፋት ተያይዘናል። ጥረታችን ፍሬ እያስገኘ ለግባችን መብቃት እንችል ዘንድ የአዲሱ የፖለቲካ ሥርዓት መሟላት አስፈላጊ ሁኔታ ነው።

በዚህ መሠረት እኛ የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ፡

—ሙሉ የሥልጣን ባለቤትነታችን የሚገለጽበትን፤

—የራሳችንን ዕድል በራሳችን በመወሰን የአገራችን አንድነትና የብሔረሰቦች እኩልነት የሚረጋገጥበትን፤

—መሠረታዊ ነፃነቶችና መብቶች የሚጠበቁበትንና ግዴታዎች የሚከበሩበትን፤

—ለሶሻሊዝም አስተማማኝ መሠረት የሚጣልበትንና የሚገነባበትን፤

—ለዓለም ሰላም፣ ለፍትሕ፣ ለዲሞክራሲና ለማኅበራዊ እድገት ተገቢ አስተዋጽኦ ለማድረግ የሚያስችለውን፤

የኢትዮጵያ ሕዝባዊ ዲሞክራሲያዊ ሪፑብሊክ የሚመሠረትበትንና የሚተዳደርበትን ይህን የአገሪቱ የበላይ ሕግ የሆነውን ሕገ መንግሥት በ፲፱፻፸፱ ባደረግነው ውሳኔ ሕዝብ አጽድቀናል።

# መቅድም

እኛ የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ አሁን ከምንገኝበት ኋላቀርነት ወደ ከፍተኛ የእድገት ደረጃ ለመሸጋገር ፣ የዘመናት አኩሪ ታሪካችንን መሠረት በማድረግ ፍትሕ ፡ እኩልነትና ማኅበራዊ ብልጽግና የሰፈነበት ሶሻሊስት ኅብረተሰብ ለመገንባት በከፍተኛ አብዮታዊ ትግል ላይ እንገኛለን ።

ኢትዮጵያ የጥንት ገናና ሥልጣኔ ባለቤት የሆነችና ለብዙ ሺህ ዓመታት ሳይቋረጥ የቆየ ነፃ መንግሥት ያላት አገር ናት ።

የኢትዮጵያ መንግሥት በሐውርታዊ ሆኖ የኖረ ነው ። የአገሪቱ ብሔረሰቦችና ልዩ ልዩ ማኅበረሰቦች በባህል መወራረስ ፣ በፈለሳ ፣ በንግድና በመሳሰሉት እንቅስቃሴዎች ፣ በሰላምና በጦርነት ጊዜ ተሳስረው የኖሩ ናቸው ። ስለዚህ የኢትዮጵያ ረጅም የነፃነት ታሪክ የብሔረሰቦቿ የጋራ ሕልውናና የጋራ ትግል ታሪክ ነው ።

ኢትዮጵያ የአፍሪካ ፡ የእስያና የአውሮፓ አህጉሮች መገናኛ በሆነ ስትራቴጂያዊ አካባቢ የምትገኝ፣ የታላላቅ ወንዞች መነሻና ለም አገር በመሆኗ ባዕዳን በወረራ ሊይዟትና ሊከፋፈሉዋት ሞክረዋል ። በተለይም ካፒታሊዝም በምዕራብ አውሮፓ ካቆጠቆጠበት ከ፲፮ኛው ምዕተ ዓመት ጀምሮ ቅኝ ገዥዎች በቁጥጥራቸው ሥር ሊያደርጓት ተደጋጋሚ ሙከራ አድርገዋል ። ይሁን እንጂ ወራሪዎችና ቅኝ ገዥዎች በየዘመኑ የሰነዘሩትን ጥቃትና አፃራሪቱን ለመያዝ ያደረጉትን ሙከራ ሁሉ ሕዝቡ በቆራጥነት እየመከተ ድል ሲያደርግ ኖሯል ። ካፒታሊዝም ወደ ሞኖፖል ደረጃ በተሸጋገረበትና ኢምፔሪያሊስቶች ዓለምን ለመቀራመት በተነሳሱበት ወቅትም አልተበገረችም ። ይልቁንም በ፲፰፻፹፰ በጊዜው ዘመናዊ በነበረው የቅኝ ገዥ ጦር ላይ የተቀዳጀችው ታላቁ የዓድዋ ድል በዓለም ፀረ ኢምፔሪያሊስት ትግል ልዩ የነፃነት ተጋድሎን ክብርና አኩሪ ታሪክን አጐናጽፏታል ። በአርበኞቿ የአምስቱ ዓመታት ትግልና መሥዋዕትነትም በፋሺዝም ወረራ ላይ ድልን በመቀዳጀት በታሪክ ተረጋግጦ የቆየውን የነፃነት አርማዋን ከማውለብለብ የሚገታት ኃይል አለመኖሩን እንደገና አስመስክራለች ።

የኢትዮጵያ ሕዝብ ከጠላት የሚሰነዘርበትን ጥቃት እየመከቱና ተደጋጋሚ ድሎችን እየተቀዳጀ አልደፈር ባይነቱንና ለነፃነት ቀናኢነቱን እያረጋገጠ አገሩን አስከብሮ ኖሯል ።

በሌላ በኩል የኢትዮጵያ ሠርቶ አደር ሕዝብ በዚህ የረጅም ዘመን ታሪኩ በልዩ ልዩ ማኅበረ ኢኮኖሚያዊ ሥርዓቶች ውስጥ የተጓዘ ሲሆን በዚሁ ሂደት ላይ መራራ የመደብ ጭቆናና ግብዝበዛ ጊዜ አሳልፏል ። በተለይም በፊውዳሉ ሥርዓት ውስጥ የነበረው ግንኙነት ገበሬውን እስከፊ በሆነ የጭቆና ቀንበር ሥር ጥሎት እንደነበር ይታወቃል ። ፊውዳሎች በየጊዜው በመካከላቸው በሚያነሱት ግጭትና ጦርነትም ሕዝቡ ሲማገድ ፡ የጉልበቱ ውጤት የሆነውን ምርት በልዩ ልዩ መንገድ ሲቀማ ፡ ረሃብ ፡ በሽታና እልቂት ሲፈራረቁበት ኖሯል ።

ከካፒታሊዝም ማቆጥቆጥ ጋር ደግሞ በሥርዓቱ ውስጥ ቅራኔው እየተካረረ መጥቶ ሕዝቡ ጭቆናውን ሊሸከመው ከማይችልበት ደረጃ ላይ በመድረሱ ተራማጅ የኅብረተሰቡ ክፍሎች በከፈሉት ከፍተኛ መሥዋዕትነት የፊውዳሉ ሥርዓት ሊገረሰስ ችሏል ። በዚህ መሠረት በ፲፱፻፷፮ የተቀጣጠለው ሕዝባዊ አብዮታችን ለዛሬው ሕዝባዊ ልዕልና በር ሊከፍት በቅቷል ።

አብዮቱ በተቀጣጠለበት ወቅት የተደራጀ ግንባር ቀደም አመራር ሰጪ አካል ስላልነበረ ፣ የሠርቶ አደሩ ሕዝብ ወገን ከሆነው የመለዮ ለባሹ ክፍል የተውጣጣው ጊዜያዊ ወታደራዊ አስተዳደር ደርግ ትግሉን አስተባብሮ መምራት ጀመረ ። ከዚያም የዘውድ አገዛዝን በማስወገድና በተከታታይ ልዩ ልዩ አብዮታዊ እርምጃዎችን በመውሰድ ለአዲስ ሕዝባዊ ሥርዓት መሠረት ጣለ ። የገጠር መሬት ፣ የከተማ ቦታና

